


# የቦሌ ክፍለ ከተማ ወረዳ 01 ፓርቲ ቅ/ ጽ/ቤት

# የአደረጃጀት ዘርፍ

# የ2017 በጀት አመት የተከለሰ ዕቅድ

መስከረም /2017ዓም

አዲስ አበባ

## ማውጫ

## I. መግቢያ

የቦሌ ክፍሌ ከተማ ወረዳ 01 አደረጃጀት ዘርፍ በ2016 በጀት ዓመቱ ከዝግጅት ምእራፍ ጀምሮ በ2015 በጀት አመት ግምገማ መነሻ በማድረግ በ2015 በጀት አመት የተገኙ ድሎችን በማስቀጠልና የታዩትን ክፍተቶችን በማረም መደበኛና መደበኛ ያለወሆኑ ወቅታዊ ተልኮዎች በወረዳ ደረጃ ተግባራት ፖለቲካዊ ትርጉም ተስጥቶት ብልፅግና ፓርቲ በሀገራችን ኢኮኖሚያዊ፤ፖለቲካዊ፤ማህበራዊና ዲፕሎማሲያዊ ዘርፎች ተጨባጭ ውጤቶችን ያስመዘገበቤት ህበረተሰቡ በግልፅ በማስመዝገብ ህዝቡ ከመንግስት እና ከፓርቲያችን ጋር የሚያቀራርቡ የፖለቲካ ስራዎች ዕቅድ በማዘጋጀት ቅድሚያ መሰጠት ያላባቸው ጉዳዎችን በመለየት ቅድማ ተሰጥቶት በየደረጃው ከሚገኝ መዋቅራችን ጋር በ2016 በጀት አመት እቅድ ላይ የጋራ መግባባት ላይ በመድረስ ወደ ተግባር መግባታችን ይታወቃል፡፡

በመሆኑም የብልጽግና ፓርቲ የህዝባችንን ሁለንተናዊ የኢኮኖሚ፣ የፖለቲካ እና የዲሞክራሲ ህብረብሔራዊ አንድነቱን ህዝባችን ለውጡን እድያጣጥሙና ብልጽግናን ለማረጋገጥ የመደመር እሳቤ ለአመራራችንና ለአባላችን ብሎም ለህዝባች ብልፅግና ያመጣቸውን ልማትና የአገር እድገት በማስረዳት ህዝቡ ለልማቱ የኔነት ስሜት የማረጋገጥ የሀገር ግንባታ ስራችንን ለማሳለጥ የሚያስችሉ በርካታ ተግባራት ተከናውነዋል፡፡

በአጠቃላይ በህብረተሰባችን ውስጥ የሚታየው የዕድገት ፍላጎት በዓይነትም በመጠንም በከፍተኛ ደረጃ እያደገ ከመሆኑም ባሻገር የተለዋዋጭነት ምጣኔው በጣም ፈጣን መሆኑ ብዙ መዋቅራችንና ህብረተሰቡ ዘንድ በተለያየ ጊዜ የሚፈጠሩ ወቅታዊ ብዥታዎችን በመቅረፍ የተቀራረበ አመለካከት እንዲኖር ለማድረግ የተለያዩ ወቅታዊና መደበኛ መድረኮችን እስከ ብሎክ ድረስ በማዘጋጀት የህብረተሱን አጠቃላይ ስሜቱ በመረዳት እና የፓርቲያችንን የመደመር እሳቤ እና የብልጽግና ፓርቲ እሴቶች ላይ ግልጽ የሆነ ግንዛቤ በመፍጠር እና በማስያዝ በኩል በርካታ ስራዎችን ማከናወን ተችሏል፡፡ በተለይ በየደረጃው ያሉ ተቋማት መ/ፓርቲ፣ ህዋስ መሳዉ አባላችን እና ሌሎች አደረጃጀቶች የሰለም ሰራዊት እንድሁም በየደረጃው የሚገኙ የስቨክ ማህበራት፤ብሎክ አጀረጃጀት ተቋማት እንዲጠናከሩ የተሰራ በርካታ ስራዎች በኖሩም እነዚህን ተቋማት በተሟላ መንገድ ወደተግባር በማስገባት እና እራሳቸውን ችለው እንዲቆሙ ከማደረግ አንጻር በቀጣይ 2017 ዓ.ም በጀት አመት በማጠናከር እንደሚያስፈልግ በመረዳት የ2017 የበጀት አመት መነሻ እቅድ ተዘጋጅተዋል፡፡

## ክፍል አንድ

# 1. *የዕቅዱ መነሻ ሁኔታዎች ትንተና*

## 1.1. *መነሻ ሁኔታዎች*

### *1.1.1. ዓለማዊ እና ቀጠናዊ ሁኔታ እንደመነሻ*

*ሀገራችን ኢትዮጵያ እንደ አንድ አለም አቀፍ የፖለቲካና የኢኮኖሚ ተዋናይ ሀገር በአለም አቀፍና ቀጣናዊ ጉዳዮች በሚኖራት ድርሻ እንዲሁም ባላት ስትራቴጂካዊ አቀማመጥ፣ ታሪካዊ ዳራና ነባራዊ ሁኔታ፣ በተለይም ደግሞ ከሀገራዊ ለውጡ ወዲህ እያበረከተች ባለችው ፖለቲካዊና ዲፕሎማሲያዊ አስተዋፆ የተነሳ በበጎም ይሁን በክፉ አለማዊና ቀጠናዊ ሁኔታዎች ተፅዕኖ ያሳድሩባታል:: በተመሳሳይ ሁኔታ ከተማችን አዲስ አበባም በሀገር ደረጃ ባላት ድርሻ ብቻ ሳይሆን በአለም አቀፍ የዲፕሎማሲ መናሃሪያነቷና የበርካታ አለምአቀፋዊ፣ አህጉራዊና ቀጠናዊ ተቋማት መቀመጫነቷ የሚያሳርፍባት ጫና ቀላል ግምት የሚሰጠው አይደለም:: በመሆኑም በ2016 በጀት አመት የቦሌ ክፍለ ከተማ ወረዳ 01 ብልፅግና ፓርቲ ቅ/ጽ/ቤት የፓርቲ ስራዎች እቅድ አቅደው በዚህ ዓለማዊ እና ቀጠናዊ ሁኔታ ውስጥ በክፍለ ከተማችን አንፃር ቀጥተኛ ትስስር ባላቸው ጉዳዮች ላይ ማተኮር እንደ አንድ መነሻ መውሰዱ ተገቢ ይሆናል::*

*ይህንን አለማዊ ሁኔታ በመገንዘብ በተለይ የኑሮ ውድነትን ለማረጋጋት ለዘላቂ የዋጋ መረጋጋት አስተዋፆ በሚያመጣ ሁኔታ ትኩረት ሰጥቶ በመስራት የዜጎችን ሥራ አጥነት በመቀነስ አምራች ዜጋን በማበራከት ህብረተሰቡ በምግብ ራሱን እድችል የሌማት ቱሩፋት ተጠቃሚ እድሆን በስፋት ግንዛቤ በመስጠት ምግቤ ከጓሮዬ የምለውን መሪ ቃል ተግባራዊ እድሆን እድሁም የቅዳሜና እሁድ (ሰንደይ)ገብያን በመጠቀም የምንችልበት እድሉ በመኖሩ የተሻለ ያደርገዋል::*

### 1.1.2. *ሀገራዊ ሁኔታ እንደመነሻ*

*የሀገራችን የፖለቲካ ልምምድ በውይይትና በሀሳብ ብልጫ ላይ የተመሠረተ ሀገር ግንባታን ከመከተል ይልቅ በአብዛኛው በኃይልና በጉልበት የሚፈፅምና መገዳደልን ማዕከል ያደረገ ሆኖ ቆይቷል:: ለዚህ በዘላቅነ ችግሩን ለመፍታት የዴሞክራሲ ግንባታ ልምምድ በማሳደግ ሀገር በቀል ልምምዶች የመቻቻል ፣የአብሮነትን ባህል በማሳደግ የመገዳደል የአስተሳሰብ መቅረፍ የነጠላ ትርክት ወደ ወል ትርክ በመቀየር ስልጣን በኃል ሳይሆን በምርጫ ብቻ የህዝብ እውንታን ሳያገኙ ወደ ሥልጣን በድሃ ደምና አጥንት ለመምጣት የሚደረገው ሙከራ ለአገራችን ውድቀት እንጅ እድገት እዳልሆነ ተረጋግጧል:: ከዚህ አኳያ ፓርቲያችን የፖለቲካና አቅም ግንባታ ሥራችን*

በሳደግ በጥልቀት በመገምገም በሀገራችንን ሥር የሰደደ ዴሞክራሲ ለመገንባትና ተመጠጣኝ ትግል ለማድረግ ዉሳኔ ማሳረፉ ይታወሳል። በመሆኑም መዋቅራችን የአገራችን ፖለቲካ ሁኔታ በመረዳት የፓርታችን እሳቤ ለማሳካት ከአመራሩ ጎን በመሰለፍ የ2017 በጀት አመት እቅድ ግቡን እንዲመታ ርብርብ ማድረግ ይኖርበታል።

## 2.2 የወረዳችን ሁኔታ እንደመነሻ

ወረዳችን ፓርቲያችን ብልፅግና የከተማችን ዘርፈ ብዙ ችግሮች የሚፈቱበትን ስልት ቀይሶ ነዋሪዎቿን አሳታፊና ተጠቃሚ የሚያደርግ ሥርዓት መገንባት መጀመሩ ይታወቃል። ቦሌ ክፍለ ከተማ ወረዳ 01 ከልማት፣ ከመልካም አስተዳደርና ከአገልግሎት አሰጣጥ ጋር የተያያዙ ውስብስብ ችግሮችን በመፍታት ለወረዳ ነዋሪዎች ምቹ ለማድረግ የሚከናወኑ ተግባራት ዉጤታማ መሆን ጀምረዋል በ2016 በጀት አመትም አንፀባራቅ ደሎችም ተመዝገቧል። የወረዳችን ገጽታ የቀየሩና ብልፅግናችን አይቀሬ መሆኑን ያሳዩ ትላልቅ ፕሮጀክቶች ተገንብተዋል። አነስተኛና መካከለኛ ገቢ ያላቸዉን ነዋሪዎች ኑሮና ህይወት የሚቀይሩ ሰዉ ተኮር ሥራዎች አመርቂ ዉጤት ተመዝግቦባቸዋል። በ60 እና የ90 ቀናት ዕቅድ የተከናወኑ ተግባራት ሞዴል ወረዳዎችንና ሞዴል ብሎኮች መፍጠር ተችሏል የሥራ  የባህል በማሳደግ የምሽት ሥራ በተለያዩ ሴክቴሮች መጀመሩ ማህበራዊ፣ ኢኮኖሚያዊና ፖለቲካዊ ስብራቶችን በመጠገን፣ የባህል ሽግግር በማምጣትና ከአመራር እስከ ነዋሪ የስራ ባህልን በማሻሻል ውጤት የተገኘባቸው አመት ነው ብሎ መውሰድ ይቻላል ። በዚህ በጀት አመት ሌላው  በክፍሌ ከተማችንን የሰው ቶኮር ሥራችንን የኮሪደር ልማት አፈፃፀም፣ ጥራቱና ስፋቱ የአመራርና የህዝብ ቅንጅት የባለ ሀብት ተሳትፎ የተሳካ ውጤት የተገኘበት ስራ መሆኑን።

እነዚህ ስኬቶች ለክፍሌ ለከተማችን ነዋሪ ጉስቁልና ምክንያት የሆኑ ኢኮኖሚያዊ ችግሮች እና የኑሮ ጫናውን ለመቅረፍ የመልካም አስተዳደርና ብልሹ አሰራሮችን ደግሞ ትርጉም በአለው መልኩ በመፍታት መልካም አፈጻጸሞችን ወደ ወረዳዎች በማስፋት በተጨማሪ የሥራ ዕድል ፈጠራን ማጠናከር፣ የለማት ቱሩፋት ተግባር በማስፋፋት ፕሮጀክቶችን የመፈጸም አቅምን ማሳደግ፣ መንግስታዊ አገልግሎቶችን የማሻሻል የህዝብ እርካታ መፍጠር፣ በሌብነት ላይ የተጀመረውን ትግል ማጠናከር፣ አሁን የተጀመረው የመልካም አስተዳደር ችግሮቸን መፍታት የአገልግሎት አሰጣጥ እርካታ ማሳደግ።

## 1.1.3. የመዋቅራችን ሁኔታ እንደመነሻ

### 1.1.4.1. በየደረጃዉ ያለዉ የአመራራችን ሁኔታ

የወረዳ አመራር መደበኛ በየጊዜው የሚቀያየሩ ሀገራዊ ሁኔታዎችን ግምት ውስጥ በማስገባት ጠንካራ የአመራር ስምሪት በመስጠት የ90 እና የ60 ቀናት ዕቅድ እና ኮሪደር ልማት ስራዎችን ከመደበኛ የመንግስትና የፓርቲ ስራዎች ጋር በማቀናጀት፣ የኮሪደር ልማት ስራዎች በማካተት በየደረጃው የተሰጡ ሀላፊነቶችን መሰረት በማድረግ ተግባራት በታቀደው አግባብ እንዲፈፀሙ ሊያደርግ የሚችል የስራ ክፍፍል በማድረግና ዋና ዋና ትኩረት የሚሹ ተግባራትን ተከፋፍሎ በመምራትና በማስተባበር ስራዎች ተሳስረው እንዲፈፀሙ በሚያደርግ የተቀናጀ አመራር አሰጣጥ የበጀት አመቱ ውጤታማ እንዲሆን አስችሏል፡፡ የበታች አመራሩን በተደጋጋሚ በቀጥታ በማግኘት በወቅታዊ አጀንዳዎች ላይ ግልፀኝነት መፍጠርና የተልዕኮዎችን ግልፅነት መፍጠር የተሰራው ስራ የተሳካ ተግባር ነበር፡፡ ወቅታዊ ሁኔታን በማወቅና በመተንተን ይህን የሚመጥን የፖለቲካ ስራ በመስራት ጥንካሬዎችን የማስቀጠልና አሉታዊ ዝንባሌዎችን ደግሞ የማረም አቅጣጫ ተከትሎ እየተሰራ ይገኛል፡፡ በሌላ በኩል ችግሮች ተከስተው ሲገኙም ችግሮች በማይባባሱበት አግባብ እንዳይስፋፉ የማድረግና ከዚህም ልምድ በመዉሰድ ዳግም እንዳይከሰቱ የሚያስችል አመራር በመስጠት በየደረጃው የሚገኘውን አመራራችን በመደገፍ የማስፈፀም አቅምን የማሣደግ ስራ መስራት ተችሏል፡፡

አስተባባሪ ኮሚቴውን ጨምሮ በወረዳ ያለው አመራር የከተማ ግብርና እና የሌማት ትሩፋት ስራዎችን ዉጤታማ ለማድረግ መዋቅራችንንና የተለያዩ የህብረተሰብ ክፍሎችን በማወያየት ያስገኘው ተስፋ ሰጭ ውጤት የሚያበረታታ ነው፡፡ ታችኛው መዋቅር ማለትም ብሎክ ድረስ ወርዶ ቀጥተኛ ድጋፍ እያደረገ መሆኑም በጥንካሬ የሚታይ ነው፡፡ በከተማችን ያለውን ባለህብትና መላውን ማህበረሰብ በማስተባበር የተሰሩ ሰው ተኮር ተግባራት በህዝባችን ዉስጥ የመረዳዳትና የመተጋገዝ ባህል እንዲጠናከር እና ወንድማማችነትና እህትማማችነት እንዲጎለብት አድርገዋል፡፡ የከተማችንን ሰላምና ደህንነት አስተማማኝ ከማድረግ አኳያ ነዋሪዎችን በማደራጀትና ህዝባዊ ሰራዊቱን በተገቢው መንገድ አሰልጥኖ በማሰማራት ህዝቡ የራሱንና የከተማውን ሰላም እንዲጠብቅ የሚያስችል ጠንካራ የአመራር ስምሪት በመስጠትና ድጋፍና ክትትል በማድረግ የተሳካ ስራዎችን መስራት ተችሏል፡፡ የከተማችን ህዝብ አንገብጋቢ የሆኑ ኑሮ ውድነትና ሥራ አጥነት ለመቀነስ የተሰራዉ ሥራ ችግሩን በሚመጥን ደረጃ መፍታት እንዲቻል የከፍተኛ አመራሩ ትኩረት ጥረት የሚያበረታታ ነው፡፡ ህገ ወጥ ግንባታዎችን እና ህገ ወጥ የንግድና የስራ እንቅስቃሴዎችን ወደ

ስርዓት ለማስገባት እና የጽንፈኛ ኃይሎችንና የሌሎች ጸረ ሰላም ኃይሎችን እኩይ ተግባር ለማክሸፍ እየተደረገ ያለው ትግል ውጤት አስመዝግቧል።

በአንጻሩ ደግሞ የህዝብ አገልግሎት አሰጣጥ አለመሻሻል፣ ሌብነትና ጽንፈኝነት አሁንም ያልተሻገርናቸዉ በሁሉም ደረጃ ባለው አመራር የሚታዩ ችግሮች መኖራቸዉ ሲታይ በአዲሱ በጀት አመት ለአመራር ግንባታ ልዩ ትኩረት መስጠት እንዳለብን መገንዘብ ይቻላል። በአመራራችን ውስጥ የአፍራሽ ኃይሎችን አስተሳሰብ የሚጋሩ እንዳሉ ይታወቃል። ሌላው ነዋሪ የሚያነሳው በማስመሰል የጠላትን አጥፊ መልዕክቶች የሚያራግቡ አመራሮች በሁሉም ደረጃ አሉ። በሶሻል ሚዲያዉ ተገቢውን ትግል የማያደርጉና አንዳንዴም አንዳንድ አመራሮች ዛሬም ከብልፅግና አስተሳሰብ ባፈነገጠ መልኩ ጽንፍ ይዞ የብሄር ጠበቃ መሆንና ብልሽት ዉስጥ ሲገባ ብሔርና አካባቢን መደበቂያ ዋሻ የማድረግ አዝማሚያ እንዲሁም ድርጊቶችም አሉ። ከላይ እንደተገለፀው በሁሉም ደረጃ የሚገኘው አመራራችን በሰራቸው ስራዎች ብልፅግና ለህዝብ ቃል በገባው መሰረት በርካታ ለውጦችን ማስመዝገብ ተችሏል። ይህም ሆኖ ግን የብልፅግና ሣንካ የሆነውን አገልግሎት አሰጣጥ፣ ሌብነትና ብልሹ አሰራሮችን በማስተካከል የህዝብን እርካታ መፍጠር አልተቻለም። ከዚህ አኳያ በሁሉም ደረጃ የሚገኘው አመራራችን ሀላፊነቱን በአግባቡ መወጣት አለመቻል፣ ራሱንና የሚመራውን ተቋም በአገልግሎት አሰጣጥ የተሳካለት አለመሆኑን ሌብነትና ብልሹ አሰራሮችንም ከማስተካከል አኳያ መሰረታዊ ጉድለቶች አሉበት። ጠንካራ ትግል አለማድረግ፣ ችግሩን በሚመጥን ልክ መፍትሄ ሊሰጥ የሚችል ውጤት ማምጣት አለመቻል ጉድለቶች አሉ።

### *1.1.4.2. የመሳዉ አባላችን ሁኔታ*

የወረዳችን የብልጽግና ፓርቲ አባላት እስከ አሁን የደረስንበት 8193 አባል 36 መሰረታዊ ድርጅት 223 ህዋስ የሚሆነዉ ተደራጅቶ በኮንፈረንስና ሌሎች የአቅም ግንባታ መድረኮች በመገኘት እርስ በእርስ ለመገንባባትና የፓርቲያችንን አደረጃጀት ለማጠናከር ጥረት የሚያደርግ ነው። አባላችን ከቁጥር ባለፈ ብልጽግና ፓርቲ በአዲስ አበባ ከተማ ውስጥ ህዝባዊና ተቋማዊ መሰረት እንዲይዝ ከፍተኛ አስተዋፆ እያበረከተ ስለመሆኑ በርካታ ማሳያዎች አሉ።

በከተማችን በተገባው ቃል በጀት ዓመት ለተመዘገቡ የልማት፣ የመልካም አስተዳደርና የአገልግሎት አሰጣጥ ማሻሻል እንዲሁም የተረጋጋ ሰላምና ጸጥታ መስፈን የተጫወተዉ ሚና ተኪ የሌለዉ ነው። አባላችን በመደበኛና ወቅታዊ የንቅናቄ ተግባራት ላይ ከፊት ሆኖ ህዝቡን በማስተባበር፣ በተለያዩ የመንግስትና የህዝብ አደረጃጀት ኮሚቴዎች ውስጥ አመራርና አባል በመሆን የፓርቲያችን የመሪነት ሚና እንዲረጋገጥ ያደረገዉ ጥረትና የተገኘዉ ዉጤት አበረታች እንደሆነ ተገምግሟል።

ከወቅታዊ አጀንዳዎች ጋር ተያይዞ በተለያዩ የከተማችን ህብረተሰብ ክፍሎች ዘንድ የሚስተዋሉ ብዥታዎችን ሊቀርፍ የሚችል ግንዛቤ በመፍጠር፣ የማዕድ ማጋራት፤የአቅም ደካማዎችን ቤት እድሳት ስራዎችን በማስተባበር እና ሌሎች ሰዉ ተኮር በጎ ፈቃድ ሥራዎችን በኃላፊነት በመወጣት መላ አባላችን በአርዓያነት ሊጠቀስ የሚችል ዉጤታማ ስራ ሰርቷል፡፡ የ60 እና የ90 ቀናት ዕቅድ አፈጻጸም ዉጤታማ እንዲሆን በማድረግ ረገድም የአባላት ተሳትፎ ላቅ ያለ ነበር፡፡ የከተማችን ነዋሪ ተደራጅቶ የአካባቢውን ሰላምና ፀጥታ በመጠበቅ ባስመዘገበው ስኬት ውስጥ የአባላችን ሚና ግንባር ቀደም ድርሻ አለው፡፡

በአጠቃላይ አባላችን በአረንጓዴ አሻራና የአከባቢ ፅዳት በበጀት አመቱ ከሚከናወኑት የኮሪዶር ልማት ጋር ተያይዘው ለሚደረገው እንቅስቃ ግንባር ቀደም ሆነው ልማቱን በአስተሳሰብ በመቀበል ሌሎችም እድቀበሉ በማስተባበር እንዲሁም ልማቱ እዲሳለጥና በታቀደለት ጊዜ እንዲጠናቀቅ የሚሰሩት ባለሙያ የማበረታታት ተግባራትም አከናወኗል ወቅታዊ እና መደበኛ ተግባራትን በራሱ ተነሳሽነትና በፈጠራ ታጅቦ ዉጤት ሊያመጣ በሚችል አግባብ ከመስራት ተስፋ ሰጪ ውጤቶች ታይቷል፡፡

### 1.1.4.3. የአደረጃጀቶቻችን ሁኔታ

በየደረጃው ጠንካራ የፓርቲ አደረጃጀት በመፍጠርና በማጠናከር የፓርቲ ተልዕኮዎችን በአደረጃጀቶች እንዲፈፀሙ ማድረግ የዘርፋችን ቁልፍ ግብ ነው፡፡ ከዚህ አንፃር በ2016 በጀት አመት አደረጃጀቶችን በአሰራርና በተግባር ውጤታማ እንዲሆኑ መፈፀም ችለናል፡፡ በበጀት አመቱ በወረዳችን ጠንካራ የፓርቲ አደረጃጀቶች የተፈጠረ ስለመሆኑ ኦዲት የማድረግ ስራ ተሰርቷል፡፡ የበለጠ ጥራቱን ለማስጠበቅ በስነ-ምግባርና ኦዲት ኮሚሽኑ ጋር በመቀናጀትም ኦዲቲንግ ስራ ተሰርቷል፡፡ ከኦዲት ግኝቶቹ በመነሳት ጉድለቶችን ለማረምና መልሶ በማደራጀት ጠንካራ የማስተካከያ ስራ በመስራት በሂደቱ በነበሩ ጉድለቶች ላይም ተጠያቂነትንም ማረጋገጥ ተችሏል፡፡

በተመሳሳይ አባላት ከአደረጃጀት ውጪ እንዳይሆኑ አደረጃጀቶች በመደበኛ ጊዜያቸው እየተገናኙ ስራዎቻቸውን በተቀመጠላቸው መርሀ ግብር መሰረት በመፈፀም ጥሩ ስራ መስራት የተቻለበት ሁኔታ እንደነበር በየጊዜው በአደረግናቸው ድጋፍና ክትትል፣ በግምገማዎቻችንና በአመቱ ማጠቃለያ ሪፓርታችንም ማረጋገጥ ተችሏል፡፡ በመደበኛ ስራዎች በውስጠ ፓርቲ ተልዕኮዎች የአፈፃፀም ግምገማ ውጤትን ማእከል በማድረግ የተሻለ አፈፃፀም ያላቸውን ግንባር ቀደም አባላት፣ መሰረታዊ ድርጅቶችና ህዋሳትን መለየት ተችሏል፡፡ ከግንባር ቀደም አባላት ደሞ ተኪ አመራሮችን በመለየት በአመራር ፑል እንዲደራጅ ተደርጓል፡፡ የመሰረታዊ ድርጀት አባላት ኮንፈረንስ

በተቀመጠው አሰራር መሰረት በማካሄድ የፓርቲውን የውስጠ ፓርቲ ዴሞክራሲን ለማጠናከር የተከናወነው ተግባርም ከባለፉት አመታት ጋር ሲነፃፀር ጥሩ አፈፃፀም የነበረው ነው። ከህዋሳት ውይይቶች አኳያም ሲታይ አብዛኞቹ ህዋሳት ውይይቶችን ሣያቋራርጡ እየተገናኙ መወያየት መቻላቸው በበጀት አመቱ በጥንካሬ የታየ ተግባር ነው። ከዚሁ ጋር ተያይዞ የተለያዩ ንዑሳን ኮሚቴዎችም የተሟላ ነው ባይባልም የተሰጣቸውን ተግባራት ለመምራት ያደረጉት ጥረት በቀጣይ ተጠናክሮ መቀጠል ያለበት ነው።

ከላይ በዝርዝር የተመለከቱት የአፈፃፀም ጥንካሬዎች እንደጥሩ መነሻ ሊወሰዱ የሚችሉ ቢሆንም በሁሉም የፓርቲው መመዘኛዎች በአመለካከትና በተግባር አንድነት፣ በውጤታማነት፣ በስነ-ምግባር አኳያ ሲታይ ጠንካራና በአሰራር የተገነባ አደረጃጀትን የመፍጠሩ ስራ በርካታ ጉድለቶች ያሉበት ነው። አደረጃጀትና አሰራር መመሪያውን መሰረት አድርጎ አለመደራጀት፣ መደበኛ ውይይት ማቋራረጥ በሱፐርቪዥን፣ በኦዲቲንግ ማረጋገጥ ተችሏል። የበሰለና ለውጥ ሊያመጣ የሚችል አጀንዳ የመቅረፅ ውስንነት እንዳለ ተረጋግጧል። የንኡሳን ኮሚቴዎች አንዳንድ ያለመደራጀትና የተደራጁትም ተግባርና ተልዕኮዎቻቸውን አውቀው ወደ ተግባር ያለመግባት ውስንንት መኖሩ ።

### 1.1.4.4. የአመራር ምዘናና ስምሪት እንደመነሻ

የአመራር ጥራትና የመፈፀም አቅም ለማሣደግ የአመራር ምዘና ማስፈፀሚያ መመሪያ ተዘጋጅቶ ስራ ላይ ውሏል። በዚህ መሰረት የአመራር ምዘና አፈፃፀምን ለማሳካት ፖለቲካዊ ትርጉም በመስጠት ፣ የጋራ ግምገማ በማድረግና የምዘና ማስፈፀሚያ እቅድ በማዘጋጀት የ2015 አፈፃፀምንና እንዲሁም የ2016 ግማሽ የበጀት አመት የፖለቲካ ምዘና በማድረግ የተተነተነ ሪፖርት መዘጋጀቱ እና አዝማሚያውን መገንዘብ መቻላችን በጥንካሬ ሊታይ የሚገባው ነው። በየ6 ወሩ የአመራር ምዘና ማከናወናችን።

በጉድለት

በውስን አመራሮች ምዘናውን በአግባቡ ከመረዳትና እንደማንኛውም የፓርቲና የመንግስት ስራዎቻችን በሁሉም ደረጃ የሚገኙ አመራሮች ትኩረት አለመስጠት ጉድለቶች ነበሩበት። ለራስ የምሰጡ ውጤት በጋሽብ ፣ ራስን ከተግባራዊ ተልዕኮ አፈፃፀም ጋር አስተሳስሮ ከማየት አለመቻል፣ የአመራር አቅም ለመገንባት የሚያስችል ጉድለቶችን ለይቶ በማሣየት በኩልም ክፍተቶች የነበሩበት መሆኑ፣

### 1.1.5 የምሁራንና የመንግስት ሰራተኞች ሁኔታ

ብልጽግና ፓርቲ በፖለቲካ ፕሮግራሙና መተዳደርያ ደንቡ እንዲሁም በአፈፃፀም ደረጃ ምሁራን በአባልነት እንዲካተቱ በተቀመጠው አቅጣጫ መሠረት በበጀት አመቱ በልዩ ሁኔታ በእቅድ በመያዝ ሙሁሩን አባላ በማድረግ የፓርታችንን አቅም በምሁር የማሳደግና በመንግስትና በፓርቲዉ የተለያዩ የኃላፊነት ቦታዎች እንዲመደቡና በሌሎች ሀገራዊ ጉዳዮች ዉስጥ አስተዋጾ እንዲያደርጉ ምቹ ሁኔታን ፈጥሯል፡፡ በወረዳችን ይሄው ተግባራዊ እየሆነ የመጣ ሲሆን በቀጣይም ጅምር ስራዎችን አጠናክሮ መቀጠል ያስፈልጋል፡፡ በምሁራን ላይ የምንሰራው የፖለቲካ ስራ ደካማ በመሆኑ የአባላት ቁጥራችን በጣም አነስተኛ እንደሆነ ይታወቃል፡፡ በትምህርት ተቋማት ከሁለተኛ ደረጃ ትምህርት ቤቶች እስከ ዩኒቨርሲቲዎች ድረስ የፖለቲካና የአደረጃጀት ሥራዎቻችንን ተደራሽነት በማስፋት የሚታዩ ክፍተቶችን ማተስካካልና ምሁራንና በአግባቡ መያዝ ይኖርብናል፡፡ በተጨማሪም የተፅኖ ፈጣር ወጣቶችን የመመል ሥራችን በተቋማዊ አሰራር መተግበር አለብን፡፡

### 1.1.6 የባለሃብቱና የንግዱ ማህበረሰብ ሁኔታ

የግል ባለሃብቱ ከጅምሩ የፓርቲያችን ደጋፊ መሆኑን ሲያሳይ የቆየ የህብረተሠብ ክፍል ነዉ፡፡ በተለይም ፓርቲያችን የሚከተለዉ የአካታችነት መርህ በተግባርም እያረጋገጠ የመጣ ስለሆነ በግል ባለሃብቱ ዘንድ ጥሩ ስሜትና ተስፋ እየሠጠዉ ይገኛል፡፡ ባለሃብቱ ሀገራችን አሁን ያለችበት ችግር ለመቅረፍ በሚደረገዉ ርብርብ የበኩሉን ሀገራዊ ግዳጅ እየተወጣ ይገኛል፡፡ በከተማችን ለሚተገበሩ የልማት ሥራ ሰው ተኮር ፕሮጀክቶች የሆኑ የበጎ አድራጎት ስራዎች ከፍተኛ የሃብት ድጋፍ እያደረገ ይገኛል፡፡

አጠቃላይ የንግዱ ማህበረሰብም በከተማችን የልማት ስራዎች ላይ ሀብት በመለገስ፣ ሰዉ ተኮር የልማትና በጎ አድራጎት ተግባራት ላይ በመሳተፍ የሚያርጉት አበርክቶ ከፍተኛ ግምት የሚሰጠዉ ነው፡፡ በከተማችን ዉስጥ በሚካሄዱ ኢኮኖሚያዊና ማህበራዊ ልማት እንቅስቃሴዎች ውስጥም የንግዱ ማህበረሰብ ሚና ጉልህ በመሆኑ በህግ አግባብ ብቻ የሚንቀሳቀሱ፣ የምርትና ሸቀጥ አቅርቦት ዕጥረት እንዳይባባስ የሚሰሩና ሸማቹን ህብረተሰብ በቅንነትና በታማኝነት የሚያገለግሉ ነጋዴዎችን በርካታ ናቸው፡፡ በአንጻሩ አንዳንድ ነጋዴዎች ምርት በመደበቅ ያለአግባብ ለመክበር በመፈለግ የገበያ አለመረጋጋትና የኑሮ ውድነትን በማባባስ በህብረተሰቡ ላይ ኢኮኖሚያዊና ማህበራዊ ጫና እንዲፈጠር ያደርጋሉ፡፡ በህገ ወጥ ተግባራት ላይ በማሳተፍ የገበያ ሥርዓት የሚያዛቡ፣ ምርት የሚሰዉሩና ለሸቀጥ እጥረት መንስኤ የሚሆኑ ነጋዴዎችም ቁጥራቸዉ ቀላል አይደለም፡፡

ፓርቲያችን በአንዳንድ ጉዳዮች ላይ ከባለሃብቶችና ከነጋዴ ማህበረሰብ ጋር ተቀራርቦ ከመወያየትና አስተዋፆአቸውን ከመጠየቅ ባለፈ ወደ ፓርቲያችን በአባልነት የሚቀላቀሉበት ሁኔታ ላይ በስፋት አልሰራበትም። ሀገሩን የሚወድ፤ ማህበራዊ ሃላፊነቱን በአግባቡ የሚወጣና ለህዝቡ ጥቅም የሚሠራ ባለሀብት እንዲበራከት የተሠራዉ ሥራ በቂ አይደለም። ባለሃብቶችና የነጋዴው ማህበረሰብ እንደማንኛውም የከተማችን ነዋሪ ብልፅግናን የመቀላቀል መብት አላቸው። ይህ ደግሞ ከፓርቲያችን ሁሉን አቃፊነት ባህሪይ የሚመነጭ ነው። በሌላ በኩል የእነዚህ የህብረተሰብ ክፍሎች ወደ ፓርቲ መግባት በአባላት መዋጮ የምናገኘውን ገቢ በከፍተኛ መጠን ያሳድገዋል። በዚህ ረገድ እስካሁን ጥቂት ጅምር ስራዎች ቢኖሩም ትኩረት ያልተሰጠው በመሆኑ በአዲሱ አመት ከፍተኛ ለውጥ የምናመጣበት መሆን ይኖርበታል።

በመደበኛነትም በባለሀብቱና በንግዱ ማህበረሰባችን ዘንድ የሚታዩ አዎንታዊ ዝንባሌዎችንና በጎ አስተዋጾአቸዉን ማጎልበትና አሉታዊ ዝንባሌዎችንና ህገ ወጥ እንቅስቃሴዎችን ማስቀረት በሚያስችል ሁኔታ የቅርብ ድጋፍና ክትትል በማድረግ ማረምና በከተማዉ ሁለንተናዊ ዕድገትና የብልጽግና ጉዞአችን ሂደት የሚያበረክቱትን አስተዋፅኦ እንዲያሳድጉ ማድረግ ይኖርብናል። ልክ በሌሎች የህብረተሰብ ክፍሎች እንዳደረግነው ሁሉ የንግዱ ማህበረሰብ አባላትን ከወረዳ ጀምሮ የሚያሳትፍ የንቅናቄ መድረክ ማዘጋጀት ይጠበቅብናል።

### 1.1.7 የ2016 በጀት ዓመት ዕቅድ አፈጻጸም እንደ መነሻ

በ2016 በጀት ዓመት በወረዳ ደረጃ የተለያዩ የፖለቲካና የድርጅት ተግባራትን አቅደን በዉጤታማነት መፈጸም የተቻለ ሲሆን በበጀት አመቱ በወረዳችን በርካታ ሰው ቶኮር ፕሮጀክቶችና በርካታ ኮሪደር አጠናቀን ቀሪዎቹን የኮሪደር ልማትም በአጭር ጊዜ ለማጠናቅ በዝግጅት ላይ እንገኛለን።

የ2016 በጀት አመት ዋና ዋና ተግባራት አፈጻጸም ለ2017 ዓ.ም ለዕቅድ መነሻ እንዲሆን እንደሚከተለዉ ቀርቧል።

- የአለፈው በጀት አመት በፓርቲና መንግስት ስራዎች ውጤታማ አፈፃፀም የተመዘገበበት አመት ሁኖ አልፏል። 2016 በጀት አመት በክ/ከተማችን ደረጃ የተለያዩ የፖለቲካና የድርጅት ተግባራትን በውጤታማነት መፈፀም በመቻላችን የፓርቲ ስራዎቻችን መልክ የያዙበትም አመት ነበር። በሌላ መልኩ የፓርቲና የመንግስት ስራዎችን በማቀናጀት የመንግስት ስራዎችን በፓርቲ አስተሳሰብ እንዲመሩ ከማድረግ አኳያም ለውጥ የመጣበት አመት ነው። 2016 በጀት አመት በፓርቲ መሪነት ወረዳ አመራሮችና አደራጀጀት ዘርፎች ኦረንቴሽን በመስጠትና በእቅዱ

ላይ ተግባቦት በመፍጠር ወደ ተግባር እንዲገባ ተደርጓል። በየደረጃው የሚገኙ የፓርቲ ተቋማትና አደረጃጀቶች ተልዕኮ በጥራትና በስኬት መፈፀም የሚችሉ እንዲሆኑ የፓርቲው አሰራርና ስርአቶችን መሰረት ተደርጎ እንዲደራጁ ተደርጓል።

በዚህ መነሻነት በበጀት አመት ማጠቃለያ ተግባሮች በመገምገም የወረዳ አመራሮች መገምገሙ እና መመዘኑ።

- በበበጀት አመቱ የታቀዱትን እቅዶች ፈፃሚ አካል ከማዘጋጀት ጀምሮ የአመራር መልሶ ማዘጋጀትና በወረዳ የአመራር የመፈፀም ብቃትና በትምህርት፣ በፆታ፣ በብሔር፣ስብጥሩን ጠብቆ ከማደራጀት የተሻለ መሆኑ።
- በወረዳ በፍታዊነትና ስብጥሩን በጠበቀ አመራር የመልሶ ማደራጀት ሥራ ተከናውኗል የወረዳ አመራር በቁጥረ 33 ሲሆን አስተባባሪ 5 ካብኔ 15 ነን ካብኔ 6 ፓርቲ 3 ምክር ቤት 2 አማካሪ 1 መሆኑ

#### 1.1.8 የ2017 የአደረጃጀት ዘርፍ እቅድ ዋና ዋና ታሳቢዎች

- በ2017 በጀት ዓመት የፓርቲንና የመንግስትን ዕቅድ ስናቅድ በአፈጻጸም ሂደት አዎንታዊም ሆነ አሉታዊ ተጽዕኖ የማሳረፍ ኃይል ያላቸዉ ታሳቢዎች ተለይተዉ የዕቅዳችን አካል እንዲሆኑ ማድረግ ተገቢ ይሆናል። አንዳንዶቹ ታሳቢዎች በ2016 በጀት ዓመት የተያዙ፣ ሳይከናወኑ የተሻገሩና አሁንም ተጽዕኖ ማሳረፍ የሚችሉ ናቸዉ። ሌሎቹ የመልካም አስተዳደር ችግሮችና ያገልግሎት አስጣጥ ችግሮችን መውሰድያስፈልጋል።
- የመልሶ ማደራጀት ሥራ በጥብቅ ዲሲፕሊን መመራት ይኖርበታል።

- የ2016 በጀት አመት እቅድ ኦረንቴሽን ከአመራራችንና ከመላው መዋቅራችን ጋር እቅድ በመገምገም የጋራ መግባባት ላይ በመድረስ ወደ ተግባር ተገብቷል
- 8193 አባላችን መገምገምና የፍረጃ ተግባር በጊዜና በወቅቱ ማከናወን
- የመ/ድርጅት 360ቱም እድመዘኑ ማድረግ የእቅድ ኦረንቴሽን በማዘጋጀት ወደ ተግባር መግባት።
- የህዋስ አመራር 892ቱም እድመዘኑ እና የእቅድ ኦረንቴሽን ማዘጋጀት ወደ ተግባር ማስገባት
- ከተቋም መዋቅራችን ባሻገር ከመላ አባላችን ጋር የበጀት አመቱ እቅዳችን እና የ2016 በጀት አመት እቅድ አፈፃፀም በመገምገም ከፓርቲ ሥራዎቻችን የነበሩንን ጥንካሬዎችን በማስቀጠል የነበሩትን ክፍተትም ለማረም ይረዳ ዘንድ በ2017 በጀት አመት እቅድ በማካተት መተግበር መቻል፡
- የበጀት አመት እቅዶቻችን ከማውቅራች ውጭ የወረዳችን ነዋሪ በየደረጃው እድንወያይ በማድረግ በ2016 በጀት አመት የነበሩ ድሎቻችን እድያጣጥሙ እድያስርፁ እድያስቀጥሉ ከህዝቡ ጋር በመግምግም የተገኙት ድሎችን በማሳደግ ለ2017 በጀት አመት እቅድ ተፈፃሚ እንድሆን

በማወያየት የጋራ መግባባት ላይ በመድረሱ የተሸለ ውጤትም ማግኘት የሚያስችል ተግባቦት መፍጠር

### 1.1.8.1 የለዉጡንና የለውጡን ቀጣይነት ማረጋገጥ

ለዉጡንና የለውጡን ቀጣይነት ማረጋገጥ አሁንም የሚቀጥል ታሳቢ ሲሆን ከዚህ አንጻር ባለፉት አመታት ያስመዘገብናቸውን ውጤቶች ይበልጥ አጠናክረን፤ ፈተናዎችን ቀንሰን የለውጡ ፍሬ የሆነውን ብልጽግና ህዝባዊና ተቋማዊ መሰረት ያለው በእሳቤና በተግባር ውጤታማነት እና በዲስፕሊን ጠንካራ ፓርቲ የማድረግ ጉዳይ ትልቁን ስፍራ የሚይዝ ታሳቢ ነው፡፡ ስለሆነም ስለ ለውጥና የለውጡ ቀጣይነት ስናስብ ቀደም ብሎ መምጣት ያለበት የፓርቲያችን ጥንካሬና ተቋማዊ ቁመና ስለሚሆን በ2017 በጀት ዓመት የፓርቲ ተቋማትን ጠንካራ የማድረግ አቅም ያለዉ በፓርቲያችን እሳቤ፣ በአሰራር፣ በአደረጃጀት፣ በሰዉ ኃይልና በቴክኖሎጂ የዳበረ የፓርቲ ተቋም መገንባት ላይ በትኩረት መስራት የሚጠበቅብን መሆኑ በታሳቢነት ተወስዷል፡፡

### 1.1.8.2. የተልዕኮ ግልፀኝነትና የፓርቲ ስብዕና ግንባታ

አመራሩና አባላት በፓርቲያችን አላማዎች፣ መሰረታዊያን፣ እሳቤዎች፣ መርሆዎች እና እሴቶች ላይ የጠራ ግንዛቤ፣ ቁርጠኝነትና እምነት እንዲያጎለብቱ የሚያደርግ ተከታታይ የአቅም ግንባታ ሥልጠና እንዲያገኙ በትኩረት ይሰራል፡፡ ስለሆነም የአስተሳሰብ ጥራት ተላብሶ የተግባር ዉጤታማነትን የሚያረጋግጥ፣ ፈተናዎችን ወደ ዕድል የሚቀይር፣ ከፈተና መዉጫ ብልሃቶችን እየቀየሰ መምራት የሚችል፣ የብሔር ጽንፈኝነትንና የሀይማኖት አክራሪነትን አምሮ የሚታገል፣ የተልዕኮ ግልጽነትና የፓርቲ ስብዕና የተላበሰ የአመራር ሥርዓት መፍጠር የሚገባ መሆኑ በታሳቢነት ተወስዷል፡፡

የፓርቲ ስብዕና ሌላዉ ማዕከል በአዲስ የፖለቲካ ዕይታ ሀገራዊ እመርታ ማስመዝገብ ሲሆን ይህም ከብልጽግና ፓርቲ ትውልድ ግንባታ ሥራችን ጋር በእጅጉ የተቆራኘ ነዉ፡፡ በፓርቲዉ ራዕይ፣ ዓላማና ግቦች ላይ የጋራ አስተሳሰብ የፈጠረ ብቃት ያለዉ አመራርና አባል በመፍጠር በመዋቅራችን ዉስጥ የባለቤትነት እና የማድረግ አቅም ማጎልበት ያስፈልጋል፡፡ በህዝብ ዉስጥም በተመሳሳይ ሁኔታ በአመራረት፣ በአመጋገብና በቁጠባ የባህል ሽግግር የሚያስከትል የአስተሳሰብ ለዉጥ እንዲመጣ ማድረግ የሚገባ መሆኑ በታሳቢነት ተወስዷል፡፡

### 1.1.8.3. የአገልግሎት ጥራትና ተደራሽነትን ማሻሻል

የመንግስት ተቋማት አገልግሎት ጥራትና ተደራሽነት ማሻሻል ሌላዉ የ2017 በጀት ዓመት ዕቅድ ቁልፍ ታሳቢ ነው፡፡ በከተማችን የህብረተሰቡን ተጠቃሚነት የሚያጎብቱና የአዲስ አበባን የኢትዮጵያ

ብልጽግና ተምሳሌትነት የሚያረጋግጡ ኢኮኖሚያዊና ማህበራዊ ልማት ሥራዎች እየተሰሩ ይገኛል፡፡ በሌላ በኩል በሁሉም ተቋማት ወሳኝ በሆኑና እንደ መሬት፣ ቤቶች፣ ወሳኝ ኩነት፣ ንግድ፣ ግዥ፣ ገቢ አሰባሰብ፣ የግንባታ ፍቃድና ቁጥጥር ትራንስፖርት አገልግሎት ሰጪ ተቋማት አገልግሎት አሰጠጥ መሻሻል የግድ የሚልበት ግዜ ላይ እንገኛለን፡፡ በነዚህ ተቋማት ብልሹ አሰራር በስፋት የሚተይባት ቦታ ሆኖ ይገኛል፡፡ ዋና መገለጫዎቹ ውሳኔ ያለመስጠት፣ ጉዳይ ማጓተት፣ በጉቦና ምልጃ መሥራት፣ በትውውቅና ዝምድና ማስተናገድ እና በኔትወርክና ማናለብኝነት በመንግስት ሥራ ሰዓት ቢሮ ዘግቶ በመዉጣት ዜጎችን ማንኳሰስና ማመናጨቅ ሆኗል፡፡ ይህንን ሁኔታ የሚቀይር ርምጃ በመዉሰድ መሰረታዊ ለውጥ ማምጣት የወቅቱ ፈተና በመሆኑ የመንግስትን አገልግሎት በዘመናዊ ቴክኖሎጂ አስደግፎ በማሻሻል ከአድሎ፣ ከብልሹ አሰራር እና ሌብነት ማጽዳት የሚያስችል ተጠያቂነት ማረጋገጥ ታሳቢ ያደረገ ስራ ቁልፍ ስራችን መሆኑ በታሳቢነት ተወስዷል፡፡

#### 1.1.1.1. ስራ እድል ፈጠራና የኑሮ ውድነትን መከላከል

የምርቶችና ሸቀጦች ዋጋ ንረትና የገበያ አለመረጋጋት ችግሮችን በማስወገድ የህብረተሰቡን የኑሮ ሁኔታ ማሻሻልም የ2017 በጀት ዓመት ታሳቢ ነዉ፡፡ በከተማችን ያለዉ ሥራ አጥነትና ኑሮ ውድነት በዋናነት በዝቅተኛ የኑሮ ደረጃ ላይ የሚገኘዉን የህብረተሰብ ክፍል ድህነትና ጉስቁልና እያባባሰዉ ይገኛል፡፡ ይህን ሁኔታ ለመቀየር ሁሉንም የልማት አቅሞች አሟጦ መጠቀም የሚያስችል ስልት መቀየስ ይኖርብናል፡፡

ሌላው በነዋሪው ዘንድ ከፍተኛ ቅሬታ እያስነሳ ያለው የመኖሪያ ቤት እጦት ችግር ነው፡፡ ይህንን ችግር ለመቅረፍ ከተማ አስተዳደሩ ከፍተኛ ርብርብ ሲያደርግ የቆየ ቢሆንም ከነበረው ከፍተኛ የቤት ፈላጊዎች ቁጥር አኳያ የከተማችንን የቤት አቅርቦት ችግር መቅረፍ አልተቻለም፡፡ በአሰራር ችግርም ቤቶች ያለአግባብ የተያዙበትን ሁኔታ በማስተካከል ፍትሃዊ ተጠቃሚነትን ለማረጋገጥ እየተሠራ ያለውን ጅምር ስራ በማጠናከር እንዲሁም የተጀመሩትን ሰፋፊ የቤት ግንባታ ፕሮጀክቶችን በማጠናከር የነዋሪዎችን ፍላጎትና አቅም ባገናዘበ ሁኔታ ተጠቃሚ ማድረግ ያስፈልጋል፡፡ የምርትና ሸቀጥ አቅርቦት በማሻሻል፣ የከተማ ግብርና በማስፋፋት፣ ሰዉ ሰራሽ የዋጋ ንረትና የኑሮ ውድነት መንስኤዎችን በማስወገድ፣ ለዜጎች በቂ የስራ ዕድልና የገቢ አማራጮችን መሰረት በማስፋት እና በህብረሰቡ ዘንድ የባህል ሽግግር በማምጣት ኑሮ ዉድነትን መቀነስ ሌላው ቁልፍ ታሳቢ ሁኖ እንደመነሻ ተወስዷል፡፡

# ክፍል ሁለት

## II. የእቅዱ አላማ

በ2017 ዓ.ም በየደረጃዉ የሚገኛዉ የፓርቲ መዋቅር ተፅእኖ የመፍጠር አቅሙ የዳበረ፤ ውስጣዊ ጥራት ያለው፤በዘመናዊ መረጃና በአሰራር ሥርዓቱ የተደረጀ፤ ጠንካራና የተዋሀደ፣ተቋማዊ የፓርቲ አደረጃጀት በመገንባት ተልዕኮን በተደራጀ፣ በጥራትና በውጤታማነት እንዲፈጸም ማድረግ ነው።

### 2.1. ዝርዝር ዓላማዎች

1. በጠንካራ አሰራር የተደራጀ ጠንካራ የፓርቲ መዋቅር መገንባትና ማጎልበት፣
2. በዘመናዊ የመረጃ አያያዝ ስርአታችን በጥራት የተደራጀ ስራ ላይ ለማዋል ምቹ የሆነ የመረጃ አያያዝ መፍጠርና ማጠናከር፤
3. በአመለካከትና በተግባር የተዋሐደ፣ ለውጡን በብቃት መምራት የሚችል አመራር በማረጋገጥ የፓርቲውን የመሪነት ሚና ከፍ ማድረግ፤
4. የሕዝቡን ተሳትፎ፣ ተጠቃሚነትና እርካታ ለማረጋገጥ የሚያስችል አደረጃጀት በመፍጠርና በማጠናከር የመሪነት ሚናቸውን እንዲወጡ ማድረግ፤
5. በፈጠራና በፍጥነት መርህ በመታገዝ ተልዕኮውን በውጤታማነት መፈፃም የሚችል አደረጃጃት ዕውን ማድረግ፤

### 2.2. የእቅዱ ግቦች

1. የዝግጅት ምዕራፍ ተግባራት 100% በተሳካ ሁኔታ መፈፀም ፤
2. የተናበበ፣ የተሳሰረና የተጽእኖ አድማሱ የሰፋ አደረጃጀት መፍጠርና ማጠናከር፤
3. ሁሉም አደረጃጀቶች፣ አመራሮችና አባላትን በአሰራሩ መሰረት መመዝገብ፤
4. በተከታታይ የአመራርና አባላትን የማጥራት ስራ በመስራት የፓርቲውን ውስጠ ጥንካሬ ማጎልበት፤
5. ጥራትን ማዕከል ያደረገ 159 አዳዲስ አባላትን በመመልመል የፓርቲውን መሠረት ማስፋት፤
6. የፓርቲውን የአመራር ስርዓት ለማጠናከር የሚያስችል ተኪና ኮር አመራር በየደረጃው ማፍራትና ማብቃት፤

7. የተሟላ ፣የጠራና ዘመናዊ የመረጃ ስርዓት በመዘርጋት ጥቅም ላይ ማዋል፤

8. ጠንካራ ፓርቲ ለመፍጠር የሚያስችል መመሪያዎችንና ደንቦችን ስራ ላይ በማዋል ውጤታማ የአሰራር ሥርዓት መዘርጋት፤

9. 2ኛውን መደበኛ ጉባኤ ፓርቲችንን ወደ ልዕልና በሚያሸጋግር አኳኋን ማካሄድ ፤

10. በከተማ ተቋማት የፖለቲካና አደረጃጀት ስራዎችን በውጤታማነትና በጥራት መፈፀም ፤

## 2.3. ግቦቹን ለማሳካት የሚኖሩ ዋና ዋና እና ዝርዝር ተግባራት

**ግብ 1. የዝግጅት ምዕራፍ ተግባራት 100% በተሳካ ሁኔታ መፈፀም ፤**

**ግቡን ለማሳካት የሚከናወኑ ተግባራት**

**ተግባር 1፡-** የ2016 በጀት ዓመት የዘርፉን የተግባር አፈጻጸም ውጤት ሰነድ/ሪፖርት/ መቀመርና ግምገማ ማድረግ፤

**ተግባር 2፡-** የአደረጃጀቶችና አባላት የተግባር አፈፃፀም የወል ሰንድ/ሪፖርት/ ማዘጋጀት፣ የጋራ መግባባት ላይ መድረስ እና ግምገማ ማድረግ፤የመደበኛ ስራዎችና ውስጠ ፓርቲ ተልዕኮ የተግባር አፈፃፀም ውጤት የያዘ ወል ሰነድ ወይም ሪፖርት ማዘጋጀት፣ በጋራ መገምገምና የአመራር ምዘና ማከናወን፤

**ተግባር 3፡-** በ2016 በጀት ዓመት የተግባራት አፈፃጸም ጠንካራና ደካማ ጎኖች መለየትና ማደራጀት፤

**ተግባር 4፡-** በዓመቱ መከናወን ሲገባቸው ሳይከናወኑ የተጠባጠቡ ተግባራትን መለየትና ማደራጀት

**ተግባር 5፡-** ለ2017 በጀት ዓመት የእቅድ ዝግጅት መነሻ ሁኔታዎች መለየትና መተንተን፤

**ተግባር 6፡-** ጥንካሬ በመያዝ የሚያሰፋና ክፍተቶችን የሚያረም የበሰለ፣ በውጤት ሊለካና ሊመዘን የሚችል የ2017 በጀት ዓመት እቅድ ማዘጋጀት፣ ኦሬንቴሽን በመስጠት በቂ ተግባቦት በመፍጠርና ወደ ተግባር መግባት፤

**ተግባር 7፡-** ስለእቅድ ግንዘቤ መፍጠር፣ እንዲሁም የበሰለና የራስን ተግባር ለቅሞ የያዘ የግል ዕቅድ እንዲያዘጋጁ ማድረግና በእቅድ መመራታቸውን ማረጋገጥ፤

**ግብ 2. የተናበበ፣ የተሳሰረና የተጽእኖ አድማሱ የሰፋ አደረጃጀት መፍጠርና ማጠናከር ፣**

**ግቡን ለማሳካት የሚከናወኑ ተግባራት**

**ተግባር 1፡-** በአደረጃጀትና አሰራር መመሪያ ላይ ያለውን የግንዛቤ ክፍተት መሙላት እንዲሁም ሁሉም አደረጃጀቶች በአደረጃጀትና አሰራር መመሪያ መሰረት የተደራጁ መሆናቸውን የመፈተሸ፣ መልሶ የማደራጀትና የማጠናከር ስራ መስራት፤

**ተግባር 2፡-** አደረጃጀቶችንና አባላትን ኦዲት ማድረግ፤

**ተግባር 3፡-** ሁሉም አባላት በአደረጃጀት መታቀፋቸውን ማረጋገጥ፣ ክፍተት ሲገኝ ፈጥኖ ማረም፣ /አንድም አባላት ከአደረጃጀት ውጪ እንዳይኖር ይደረጋል/፤አሰራርን ጠብቆ የሚንቀሳቀስና በማንኛውም ጊዜ የፓርቲ ተልዕኮ ተቀብሎ በተግባር ስኬት የሚያስመዘግብ አደረጃጀቶች በየደረጃው መፈጠሩንና መጠናከሩን መከታተል፣ መደገፍ፣ ማብቃት፣ ማስቀጠል፤

**ተግባር 4፡-** የፓርቲ ተልዕኮዎች ተቀብሎ በአደረጃጀቶች በመፈጸም ጥራትና ውጤታማነት ማረጋገጥ፤

**ተግባር 5፡-** ሁሉም የፓርቲ አደረደጃጀቶች ተልዕኮ በቅንነት ተቀብለው በጥራትና በውጤታማነት ሊፈፀሙና ሊያስፈፅሙ በሚችሉ እንዲሁም በመደበኛ ስራዎችና በውስጠ ፓርቲ አፈፃፀም የተሻለ ውጤት ባስመዘገቡ ግንባር ቀደም ተጽዕኖ ፈጣሪ በሆኑ አመራሮች መመራታቸውን ማረጋገጥ፤

**ተግባር 6፡-** የአደረጃጀቶች በአሰራሩ መሰረት የተሟላ አመራር ስለመኖሩ ኦዲት ማድረግና ጉድለት ሲኖር ማረም፤

**ተግባር 7፡-** በየደረጃ ያለው የፓርቲ አመራርና አስተባባሪ ኮሚቴዎች ተፅዕኖ ፈጣሪ በሆኑ አመራሮች መደራጀታቸውን መፈተሽ፤

**ተግባር 8፡-** የፓርቲ ተልዕኮዎችን መፈፀም የሚችሉ ደጋፊዎችን መለየት፣ ማደራጀትና የፓርቲ ተልእኮ እየሰጡ ማብቃት፤

**ተግባር 9፡-** አደረጃጀቶችን በውስጠ ፓርቲ ተልዕኮዎች አፈፃጸም በዓመቱ መጨረሻ መ/ድርጅት 90 በመቶ እና ህዋስ 80 በመቶ ግንባር ቀደምና ተፅዕኖ ፈጣሪ እንዲሆኑ መስራትና ማድረግ፤

**ተግባር 10፡-** የመሰረታዊ ድርጅት ንዑሳን ኮሚቴ መደራጀታቸውንና ወደ ተግባር ስራ መግባታቸውን መፈተሽ፣ ክፍተትን ማረም፣ ወደ አሰራር ማዕቀፍ ማስገባት፤

**ግብ 3. ሁሉም አደረጃጀቶች፣ አመራሮችና አባላትን በአሰራሩ መሰረት መመዘን፤**

**ግቡን ለማሳካት የሚከናወኑ ተግባራት**

**ተግባር 1፡-** የአመራርና የአባላት ምዘና ማስፈፀሚያ መመሪያ ለሁሉም አካላት ተደራሽ ማድረግና ግንዛቤ ማስጨበጥ፤

**ተግባር 2፡-** የመደበኛ ስራዎችና የውስጠ-ፓርቲ ተልዕኮ አፈፃፀም ለመመዘን ራሱን የቻለ የምዘና ማስፈፀሚያ ዕቅድ ማዘጋጀትና ኦሬንቴሽን መስጠት፤

**ተግባር 3፡-** ያሉንን አመራሮች ከ99 በመቶ እና አባላትን ከ85 በመቶ በላይ በየስድስት ወሩ ምዘና ማካሄድ፤

**ተግባር 4፡-** የምዘናው ውጤት አንድ ደረጃ ከፍ ባለ አመራር እርከን እንዲጸድቅ ማድረግ፣

**ተግባር 5፡-** የምዘና ውጤት ሁሉም መገምገምና አንዱ ከአንዱ ተሞክሮ የሚለዋወጡበት ሁኔታ መፍጠር፤

**ተግባር 6፡-** የምዘና ውጤት በምዘና ፎርማቶች በአግባቡ ሞልቶ አደራጅቶ መያዝና ሲፈለግ ጥቅም ላይ እንዲውል ማድረግ፤

**ተግባር 7፡-** ጠንካራና ደካማ ጎኖች በመለየት ለቀጣይ ምዘና በግብዓትነት መጠቀም፤

**ተግባር 8፡-** በመደበኛ ስራዎችና በውስጠ-ፓርቲ ተልዕኮዎች አፈፃጸም ውጤት ላይ በመመስረት ግንባር ቀደም አባላት ምልመላ ማከናወን፤

**ተግባር 9፡-** በምዘና አፈፃፀም ውጤት መሰረት ተኪና ኮር አመራር ምልመላ ማከናወንና የአመራር ፑል ማዘጋጀት፤

**ተግባር 10፡-** በውስጠ-ፓርቲ ተልዕኮ የተሻለ አፈፃፀም ውጤት ላስመዘገቡ አመራርና አባላት የማበረታቻ እውቅና መስጠት፤

**ግብ 4. በተከታታይ የአመራርና አባላት ማጥራት ስራ በመስራት የፓርቲውን ውስጠ ጥንካሬ ማጎልበት ፤**

**ግቡን ለማሳካት የሚከናወኑ ተግባራት**

**ተግባር 1፡-** የአመራር፣ የአደረጃጀቶችና አባላት ምዘና አፈፃጸም ውጤትን ተከትሎ የአመራርና አባላት የማጥራት ስራ መስራት፣

**ተግባር 2፡-** በውስጠ-ፓርቲ ተልዕኮ የተግባር በአፈፃጸም ሂደት ውስጥ በትግበራ በአመለካከትና በተግባር ብልጽግና ያልሆኑትን መለየትና እርምጃ መውሰድ፤

**ተግባር 3፡-** እንዲሁም የአባላት ጥራት መለኪያዎችና ደረጃ መወሰን ላይ በቂ የተግባቦት መድረክ ማመቻቸት፤

**ተግባር 4፡-** የስነ-ምግባር ብልሽት የሚታይባቸው አመራርና አባላት ላይ የእርምት እርምጃ መውሰድ፣

**ተግባር 5፡-** በበጀት ዓመቱ በየሦስት ወራት የተግባራትን የአፈፃፀም ግምገማ እንዲከናወን ይደረጋል፣ በግምገማ ሂደቱ ውስጥ የማጥራት ተግባራቱን ትኩረት መስጠት፤

**ተግባር 6፡-** በማጥራት ተግባር አፈፃፀም የታዩ ጉድለቶች በመለየት ከሚመለከተው አካላት ጋር የፖለቲካ አቅም ግንባታ እንዲያገኙ ማድረግ፤

**ተግባር 7፡-** በመደበኛ ስራዎችና ውስጠ-ፓርቲ ተልዕኮ አፈፃፀም ግንባር ቀደምና ተፅዕኖ ፈጣሪ አባላት 70 በመቶ እንዲሆኑ መስራት፤

**ተግባር 8፡-** ከግንባር ቀደም አባላት ዉስጥ 5621 ውስጥ 474 ተተኪ አመራር 19 ኮር አመራር መመልመል ከአሉን ህዋሳት ዉስጥ 223 ውስጥ 178 ግንባር ቀደም ከ223 ህዋስ ውስጥ 45 ሞዴል ማድረግ 36 መ/ድርጅት ዉስጥ 9 ሞዴል ማድረግ፤

**ተግባር 9፡-** የማጥራት ተግባር አፈፃፀም የተደራጀና ጥራት ያለው ሪፖርት ማቅረብ፤

**ግብ 5. ጥራትን ማዕከል ያደረገ 159 (ከተፅኖ ፈጣሪ ሰዎች፣65፣ ከምሁራን 84 እና ባለሀብት 10 አዳዲስ አባላትን በመመልመል የፓርቲውን መሠረት ማስፋት ተችሏል፣ አሁን ከአለን 8030 አባለት ወደ 8189 አባላት ከፍ ማድረግ ፡፡**

**ግቡን ለማሳካት የሚከናወኑ ተግባራት**

**ተግባር 1፡-** በአባላት ጥራት ማስጠበቂያ መመሪያው ላይ ለሚመለከታቸው አካላት ስልጠና በመስጠት ወጥ የሆነ ግንዛቤ ተይዞ ወደ ተግባር እንዲገባ ማድረግ፤

**ተግባር 2፡-** በመመሪያው ላይ በተቀመጠው መሰረት አባሉ ከተመለመለ በኋላ በደጋፊነት ስድስት ወር እንዲቆይ ተደርጎ የተለያዩ ተልዕኮ እየተሰጣቸው ይፈተሹ፣ በመቀጠል በስራቸው ታታሪ የሆኑና የተሰጣቸውን ተልዕኮ የፈጸሙ ከስድስት ወር በኋላ በመሰረታዊ ድርጅት አባላት ኮንፈረንስ ወደ ዕጩነት ተሸጋግሮ ተልዕኮ እንዲፈፅሙ፣ ወርሃዊ ክፍያም እንዲጀምሩ ማድረግ፤

**ተግባር 3፡-** የዕጩነት ጊዜ ከጸደቀላቸው በኋላ ስድስት ወር ከቆየ ወደ ሙሉ አባልነት እንዲሸጋገሩ ማድረግ፤

**ተግባር 4፡-** የምልመላ ስራችን ምሁራን፣ ወጣቶችና ሴቶች እንዲሁም ታዋቂና ተጽዕኖ ፈጣሪ ሰዎች ላይ ብቻ ማዕከል አድርጎ በመደበኛ ስራቸው እና በተሰማሩበት የስራ መስክ ግንባር ቀደም የሆኑና በስነ-ምግባራቸው የተመሰገኑ ላይ ትኩረት ማድረግ፤

**ተግባር 5፡-** የምልመላ ፎርሙ በአግባቡ እንዲሞላ እና በሚመለከተው ክፍል ማረጋገጥ ፤

**ተግባር 6፡-** የፓርቲውን ፕሮግራምና መተዳደሪያ ደንብ ላይ በማወያየት ግንዛቤ መፍጠር፤

**ተግባር 7፡-** በምንም መንገድ የተቀመጠውን የምልመላ አቅጣጫ በመተው ምልመላ ማካሄድ ተጠያቂነትን ማስፈን፤

**ተግባር 8፡-** ምልመላው በተቀመጠው አግባብ መሆኑን በየወቅቱ ማረጋገጥና መፈተሽ፣ ችግር ካለ በፍጥነት ማረም፤

**ግብ 6. የፓርቲውን የአመራር ስርዓት ለማጠናከር የሚያስችል 19 ኮር 474 ተተኪ አመራር በየደረጃው ማፍራትና ማብቃት ፡፡**

**ግቡን ለማሳካት የሚኖሩን ተግባራት**

**ተግባር 1፡-** የተኪ አመራር ምልመላ እና የኮር አመራር ልየታ መመሪዎች ላይ በተገቢዉ ሁኔታ ሥራ ላይ እንዲውሉ ስልጠናዎችን በመስጠት ወደ ተግባር ማስገባት፡፡

**ተግባር 2፡-** በስራው ሂደት ለሚሳተፉ አካላት ሰፊ ግንዛቤ ማስጫበጫ ስራ ማከናወን፤

**ተግባር 3፡-** ለስራው ውጤታማነት አሰፈላጊ የሆኑ የቅደመ ዝግጅት ስራዎች እንዲካናወኑ ማድረግ፤

**ተግባር 4፡-** በየደረጃው ከሚለዩ ግንባር ቀደም አባላት መካካል በመመሪው መሰረት መስፈርቱን የሚያሟሉ 474 የሚሆኑ ተኪ አመራሮች እንዲለዩና እንዲበቁ የማድረግ ስራ ማከናወን፤

**ተግባር 5፡-** በስራ ላይ ካሉ አመራሮች በመመሪያው መሰረት 19 ኮር አመራሮችን የመለየትና ለቀጣይ ተልዕኮ ዝግጁ የማድረግ ስራ መስራት፤

**ተግባር 6፡-** በተኪ አመራርነት እና በኮር አመራርነት ከሚለዩት አመራሮች መካካል የሴቶች ድርሻ ቢያንስ 40 ከመቶ እንዲሆን የሚያስችል ስራ በታቀደ መልኩ መሰራት ፤

**ተግባር 7፡-** በየደረጃው ተገቢውን ሂደት ጠብቀው የተመለመሉ ተኪ አመራሮች እና የተለዩ ኮር አመራሮች የተሟላ ግለ ታሪክ/ፕሮፋይል/ እና ዝርዝር መረጃ በሀርድና በሶፍት ኮፒ በአግባቡ ተደራጅቶ እንዲያዝና ጥቅም ላይ እንዲውል ማድረግ፤

**ተግባር 8፡-** ሁሉም የተኪና ኮር አመራር ምልመላ በመመሪያው ላይ መሰረት ሁኖ መፈፀም፤

**ግብ 7. የተሟላ፣የጠራና ዘመናዊ የመረጃ ስርዓት በመዘርጋት ጥቅም ላይ ማዋል ፤**

**ግቡን ለማሳካት የሚኖሩን ተግባራት**

**ተግባር 1፡-** በከተማ ደረጃ በለማው ሶፍትዌር ላይ ለአመራሩና ለባለሙያ በቂ ስልጠና እንዲሰጥ በማድረግ ወደ ተግባር ማስገባት፤

**ተግባር 2፡-** የአመራርና አባላት መረጃ ጥራትን ማዕከል በማድረግ ተጠቃሎ ወደ መረጃ ቋት እንዲገባ ማድረግ፣ እንዲሁም የአመራር ሲቪና ፎቶ፣ የአባላትን ፎቶ በመረጃ ቋት ተጠናቆ ማስገባት

**ተግባር 3፡-** የፓርቲ አደረጃጀቶች፣ አመራሮች፣ አባላት፣ መረጃ በኢንፎርሜሽን ኮሙዩኒኬሽን ቴክኖሎጂ የተደገፈ፣ በሚገባ የተያዘና የሚተዳደር እንዲሆን ማድረግ፤

**ተግባር 4፡-** መረጃ ቋት ውስጥ የገባ የአመራርና አባል መረጃ በየሦስት ወሩ የማጥራት ስራ መስራት፣

**ተግባር 5፡-** በተለያዩ አካላት ለሚቀርቡ የአባላት፣ አመራርና አደረጃጀቶች መረጃ ጥያቄዎች ለማስተናገድ የውስጥ አሰራር እንዲዘጋጅ ማድረግ፤

**ተግባር 6፡-** በመረጃ ቋት የመረጃ ጥራትን ለማስጠበቅ ለሚመለከተው አካል ግብረ-መልስ የመስጠት ስራ መስራት፤

**ተግባር 7፡-** በየደረጃው መረጃዎች ለጥንቃቄ ሲባል በባክአፕ እንዲያዙ ማድረግ፤

**ተግባር 8፡-** አዲስ የተመለመሉ አባላት ወደ ሙሉ አባልነት ከተሸጋገሩ በኋላ ወደ መረጃ ቋት እዲገቡ ማድረግ፤

**ተግባር 9፡-** ከፓርቲው በተለያዩ ምክንያት የሚሰናበቱ አባላት መረጃን በየፈርጃቸው በማደራጀት በመረጃ ቋት የመሰረዝ ስራ መስራት፤

**ተግባር 10፡-** በመረጃ ቋት ውስጥ የገባውን መረጃ የሚመለከታቸው አካላት መጠቀም የሚችሉበት ሁኔታ መፍጠር፤

**ተግባር 11፡-** የአባላት እና አመራር ማህደሮች እና የተለያዩ የፓርቲ ሰነዶችን በአግባቡ በማደራጀት እንዲያዙ ማድረግ፤

**ተግባር 12፡-** አሻራ የሰጡ አመራርና አባላትን መረጃ በመለያ ኮዳቸው መሰረት በመውሰድ የመረጃውን ትክክለኛነት ማረጋገጥ፤

**ተግባር 13፡-** ለፓርቲ አባላት ዲጂታል መታወቂያ እንዲያገኙ ለማድረግ የሚፈለጉ መረጃው በትክክል ወደ ዳታ ቤዝ ማስገባትና  በአባሉ የሚሸፋን ወጪዎች በፋይናንስ አሰራር መሰረት ገቢ ማድረግ፤

**ተግባር 14፡-** የዲጂታል የመታወቂያ አሰጣጥ እራሱን የቻለ መመሪያ ያለው በመሆኑ አጠቃላይ ስራው በመመሪያው መሰረት መስራት፤

## ግብ. 8. ጠንካራ ፓርቲ ለመፍጠር የሚያስችል ውጤታማ የአሰራር ሥርዓት በመዘርጋት ጥቅም ላይ ማዋል፤

### ግቡን ለማሳካት የሚከናወኑ ተግባራት

**ተግባር 1፡-** በየደረጃው ያለው አስተባባሪና የፓርቲ አመራር ኮሚቴ በተቀመጠው የግንኙነት አግባብ ሳይቆራረጥ ከተማዊ እና ከባቢያዊ ሁኔታዎችን በጥልቀት በመገምገም ችግር ፈቺ የሆነ ውሳኔዎችን በመወሰን ፣የቀጣይ አቅጣጫ በማስቀመጥ ተግባራትን መምራት እንዲችሉ ማድረግ፤

**ተግባር 2፡-** የመሰረታዊ ድርጅትና የህዋስ አመራሮች በግንኙነት ጊዜያቸው የመሰረታዊ ድርጅቱን እና የህዋሷን ሁኔታ በሚገባ በመገምገም አደረጃጀቱ ተጠናክሮ የሚወጣበትን ሁኔታ መከተል ይጠበቅባቸዋል፡፡የቀጣይ የስራ አቅጣጫ እያስቀመጡ እንዲሄዱ፣ ድክመት ባለበት የእርምት እርምጃ እየወሰዱ እየሄዱ መሆኑን ክትትል ማድረግና ተከታታይ ግብረመልስ የመስጠት ስራ መስራት፤

**ተግባር 3፡-** መሰረታዊ ድርጅት ኮንፈረንስና የሕዋስ ውይይት በተከታታይ የቋሚ ግንኙነት ጊዜያቸውን ጠብቆ በማካሄድ የአባላቱን የፖለቲካ ጤንነት የማረጋገጥ ስራ እየተሰራ መሆኑን ማረጋገጥ፤

**ተግባር 4፡-** የአደረጃጀት ንዑሳን ኮሚቴዎች አመራሮች እራሳቸውን ችለው ሥራቸውን በተቀመጠላቸው ጊዜ ሰሌዳ እየተገናኙ እንዲገመግሙ ማድረግ፤

**ተግባር 5፡-** አባሉም በህዋስ ውይይትም ሆነ በመሰረታዊ ድርጅት የአባላት ኮንፈረንስ ከአቅም በላይ የሆነ ችግር ካላጋጠመ በስተቀር ሁሉም በተገኘበት በደመቀ ሁኔታ እንዲካሄድ ማድረግ፤

**ተግባር 6፡-** የጸደቀና የታተሙ መመሪያዎችና አሰራሮች ለሁሉም መዋቅር እንዲደርስ አስፈላጊውን ክትትል ማድረግ፣ መድረሳቸውንና ስራ ላይ መዋላቸውን የማረጋገጥ ስራ መስራት፤

**ተግባር 7፡-** በመመሪያዎችና አሰራሮች ላይ ለሁሉም የፓርቲ ለአመራርና አባላት በቂ ግንዛቤ የማስጨበጫ ሥልጠና አቅም ባላቸው አመራሮች እንዲሰጥ ማድረግ፤

**ተግባር 8፡-** የአመራር ምደባዎችና ሹመቶች በፓርቲ መመሪያና አሰራር መሰረት በግልጽ በየደረጃው ባለው አስተባባሪ ኮሚቴ እየታየና እየጸደቀ ብቃትና ጥረት ማዕከል ባደረገ መልኩ ከአመራር ፑል በመውሰድ ስምሪት እንዲሰጥ ማድረግ፣ የአሰራር ክፍተት ሲፈጠርም ወዲያውኑ እንዲታረም ማድረግ፤

**ተግባር 9፡-** ፓርቲያችን በየጊዜው የሚያወጣቸው መመሪያዎችና የስልጠና ሰነዶች በሥርዓት ተደራጅተው መያዝና በየጊዜው የሥራ መመሪያ እንዲሆኑ ክትትልና ድጋፍ ማድረግ፤

**ተግባር 10፡-** በየደረጃው ያሉ አደረጃጀቶችን ለማጠናከር ለአቅም ግንባታና ስልጠና ተግባራት የሚዘጋጁ አመራርና አባላትን በግልፅ መስፈርት መለየት፣ ምልመላውን ማከናወን፤

**ተግባር 11፡-** የፓርቲው ውስጠ ዴሞክራሲን የሚያረጋግጥ ግምገማና ምዘና በተቀመጠው አቅጣጫ መስረት እየተከናወነ መሆኑን በመከታተልና መደገፍ፣ ክፍተት ካለ እንዲስተካከል ማድረግ፤

**ተግባር 12፡-** የፓርቲውን አሰራርና ደንብ የሚጥሱ አመራር እና አባላት አካላት ላይ በፓርቲው መተዳደሪያ ደንብና የአባላት ስነ-ምግባር መመሪያ መሰረት እንዲሁም የፓርቲውን ውስጣዊ ተቋማዊ አሰራር በሚያጠናክር፤ ሀላፊነት የተሞላበትና ግልፀኝነትን ያለው የእርምት እርምጃ እየተወሰደ መሆኑን ማረጋገጥ፤

**ተግባር 13፡-** በየደረጃ ያሉ የክብር አባላት የምስክር ወረቀት በመስጠት በተገቢው መንገድ በፓርቲ ስራዎች ማሳተፍና ልምዳቸውን በመቅሰም ጥቅም ላይ ማዋል፤

**ተግባር 14፡-** የስራ ሪፖርት ቅብብሎሽ በአደረጃጀትና አሰራር መመሪያው በተቀመጠው የግንኙነት አግባብ  መሰረት ወቅቱንና ጥራቱን የጠበቀ መሆኑን ማረጋገጥ፣ከታች ከህዋስ ጀምሮ ተቋማዊ አሠራሮች በመጠበቅ ውጤታማነትና ችግር ፈቺ  የሆኑ ክትትልና ድጋፎች እየተደረገ መሆኑን ማረጋገጥ፤

**ግብ 9. 2ኛውን መደበኛ ጉባኤ ፓርቲያችንን ወደ ልዕልና በሚያሸጋግር አኳኋን ማካሄድ ፤**

**ግቡን ለማሳካት የሚኖሩን ተግባራት**

**ተግባር 1፡-** ራሱን የቻለ ዕቅድና የተለያዩ ኮሚቴዎች የሚደራጁ እንዳለ ሆኖ በአደረጃጀት ዘርፍ በሚሰሩ ስራዎች ላይ ትኩረት አድርጎ መስራት፤

**ተግባር 2፡-** የጉባኤ ተሳታፊዎች ፓርቲው ባስቀመጠ አቅጣጫና አሰራር መሰረት ብቃትና ቀጣይም ተመልሶ ሊያግዙ የሚችሉ አካላት መሆናቸውን ማረጋገጥ፤

**ተግባር 3፡-** በጉባኤተኛ ምልመላ አስፈላጊነት ላይ ለአባሉ በቂ ግንዛቤ እንዲፈጠር አስፈላጊውን ድጋፍ ማድረግ፤

**ተግባር 4፡-** የጉባኤ ተሳታፊዎችን መረጃ በፎርማቱ መሰረት ማደራጀት፤

**ግብ 10. በከተማ ተቋማት የፖለቲካ እና የድርጅት ስራዎችን በተሳካ ሁኔታ መፈፀም ፤**

**ግቡን ለማሳካት የሚከናወኑ ተግባራት**

**ተግባር 1፡-** የከተማ ተቋማት የፓርቲ ስራ የሚመራበት ራሱን የቻለ የፖለቲካና የድርጅት እቅድ እንዲዘጋጅ ማድረግ፤

**ተግባር 2፡-** አደረጃጀቶች መፍጠር፣ማጠናከር፣የደከሙትን መልሶ ማደራጀት፤

**ተግባር 3፡-** ነባሩን አመራርና አባላትን በየወቅቱ በማጥራት የአባላትን ጥራት ማስጠበቅ፤

**ተግባር 4፡-** የአመራር ምዘና፣ምደባ እና ጥሩ አፈጻጸም ያላቸው እውቅና እንዲያገኙ መስራት፤

**ተግባር 5፡-** ተተኪና ኮር አመራሮችን ለይቶ ስምሪት በመስጠተ ማብቃት፤

**ተግባር 6፡-** የአባላትና አደረጃጀቶች መረጃ ወደ ዳታ ቤዝ እንዲገባ ማድረግ፤

**ተግባር 7፡-** የመሰረታዊ ድርጅት ኮንፍረንስ እና ህዋስ ውይይት ወቅቱን ጠብቆ በበቂ ዝግጅት እንድከሄድ ማድራግ፤

**ተግባር 8፡-** ህዋሳት በመልካም አስተዳደር፣ ሌብነትና ብልሹ አሰራር በወቅታዊ ጉዳዮች ላይ ሳይቆራረጥ እየተፈፀመ መሆኑን ማረጋገጥ፤

**ግብ 11 የፓርት አባላት መዋጮን በመመሪያው መሰረት በማስከፈል የገቢ አቅማችንን ማሳደግ ፤**

**ግቡን ለማሳካት የሚከናወኑ ተግባራት**

**ተግባር 1፡-** የፓርቲ አባላችን የፓርቲውን አቅም ለማሳደግ ፓርቲው ባስቀመጠው መመሪያ መሰረት የፓርቲ መዋጮ እንዲከፍሉ ማድረግ

**ተግባር 2፡-** የፓርቲያችን ደጋፊ በልዩ ድጋፍ ለፓርቲ መዋጮ እንዲከፍል በማድረግ የፓርቲውን አቅም ማሳደግ

**ተግባር 3፡-** አዳዲስ አባላት ከደጋፊ ወደ እጩ አባል ሲፀድቁ የፓርቲን መዋጩ እንዲከፍሉ ማድረግ

# ክፍል ሦስት

## III. የአፈጻጸም አቅጣጫዎች፤ ስልቶች፤ድጋፍና ክትትል፤ ሊያጋጥሙ የሚችሉ ችግሮች እና መፍትሄዎቻቸው

### 3.1. የምንከተላቸው አፈፃፀም አቅጣጫዎች

የእቅዱ ማስፈፀሚያ አቅጣጫዎች በፓርቲ ዋና ፅ/ቤት በአደረጃጀት ዘርፍ የተቀመጡ ፣ በአዲስ አበባ ፓርቲ ቅርጫፍ ፅ/ቤት መሪ እቅዲ የተቀመጡት ፣እንዲሁም የጉባኤ አቅጣጫዎች የዚህ እቅድ ማስፈፀሚያ ስልቶች ናቸዉ፡፡ ተግባበሮቻችን ስኬት በጥብቅ የፓርቲ ዲሲፕሊን ላይ የተመሰረተ የክትትልና ድጋፍ ስርዓት መዘርጋት በጣም አስፈላጊ ነው፡፡ የበጀት ዓመቱ እንደ ፓርቲ ጠንካራና ጥራት ያለው ተቋማዊ አደረጃጀት የሚፈጠርበት እና በአደረጃጀቶቻችን ግንባር ቀደም መሪነት ለሁለንተናዊ ብልጽግና መሠረት የምንጥልበት አደረጃጀቶች (የፓርቲ ተቋማት) ተፅኖ ፈጣሪ ሁነው እንዲገኙ በልዩ ትኩረት የምንሰራበት ዓመት ነው፡፡ ከዚህም በተጨማሪ የጀመርናቸውን ትላልቅ ተግባራት የምናስቀጥልበት፣ ጉድለቶችን ያለምህረት ተጠያቂነትን ሊያረጋግጥ በሚያስችል መልኩ የምናርምበት ዓመት ነው፡፡ በዚህ መሰረት፡-

- ለተግባሮቻችን ስኬት ጥብቅ የፓርቲ ዲሲፕሊን ላይ የተመሰረተ የክትትልና ድጋፍ ስርዓት መዘርጋት፤
- የፓርቲው ጠንካራና ጥራት ያለው ተቋማዊ አደረጃጀት በመገንባትና አደረጃጀቶቻችንን ግንባር ቀደም እና ተፅዕኖ ፈጣሪ በማድረግ የፓርቲያችንን የማስፈፀም አቅም የምናሳድግበት ሁለንተናዊ ብልጽግና ለማረጋገጥ የተገኙ ውጤቶችን የምናሰፋበት አመት መሆን አለበት፡፡ እንዲሁም ጥንካሬዎቻችንን መሰረት በማስያዝና በማጽናት ማስቀጠል፣ጉድለቶችን ደግሞ ያለምንም ምህረት ማረም የምንችልበት ለዚህም እንዲረዳ በፓርቲው አሰራሮችን መመሪያዎች በተግባር የማረጋገጥ አቅጣጫን መከተል በትኩረት የሚሰራበት ይሆናል፤
- ጠንካራ እና ውጤታማ የፓርቲ አደረጃጃት በመፈጠር ሁሉንም ተግባራት በግንባር ቀደምትነት እንዲያከናውን የማድረግን አቅጣጨ መካተል፤
- ፓርቲያችንን እየፈተኑ ያሉ ተግዳሮቶችን በመሰረታዊነት ሊፈቱ የሚችሉ ጠንካራ አደረጃጀቶች በመፍጠርና በተግባር ግንባር ቀደመ ሁኖ በመስራት ነው፡፡ በተለይም የህዝቡን ሠላምና ደህንነት ለማረጋገጥ፣ ሌብነትና ብልሹ አሰራሮችን በተደራጀ የህዝብ ተሳትፎ የምንቀንስበት፣ ነጠላ ትርክቶችን በማረም የወል ትርክት በህዝብ ዘንድ እንዲጎለበት መስራት ወሳኝ ነው፡፡ ስለሆነም ሁሉም ተግባሮቻችን በተደራጀ ሁኔታ እንዲፈፀሙ እንደየባህሪያቸው የማስፈፀሚያ ስልት ተነድፎላቸው ተግባራዊ የማድረግ አቅጣጨን መከተል፤

- በበጀት ዓመቱ በአደረጃጀት ዘርፍ የተያዙ ግቦችን ግብ ማሳካት እንዲቻል ሁሉም ተግባሮቻችን የሚለካ፣ የሚቆጠርና የሚጨበጥ ውጤት እንዲያመጡ በትጋት የሚሰራ ይሆናል። በተለይም የፓርቲያችንን ውስጣዊ አንድነት ለማረጋገጥ የሚያግዙ ተግባራት ላይ በማተኮር አመራርና አባላትን ማጥራት፣ በተልዕኮ ማንቀሳቀስ፣ ውጤትን ማዕከል ያደረገ ምዘና ማከሔድ፣በሁሉም እርከን ተፅዕኖ የመፈጠር አቅሙ ያደገ አደረጃጀት መፈጠር ላይ ርብርብ ይደረጋል። ከዚህ በተጨማሪ የአባላት መረጃ ሙሉ በሙሉ ወደ ዳታ ቤዝ ማስገባት፣ የአባላት መታወቂያ ስርጭት ማከናወን፣ ምልመላን በጥራት ማካሄድና ባለፈው ዓመት በአደረጃጀት መከናወን እየተገባቸው ሳይከናወኑ የቀሩ ተግባራትን ጭምር በዕቅዱ በማካተት በጥራት የመፈፀም አቅጣጫን መከተል፤
- ከላይ ለተዘረዘሩት ተግባራት ስኬት በዘርፉ ያሉ አመራሮች በተቀናጀና በተናበበ መንገድ መስራት ይጠበቅባቸዋል። ከዘርፉ ተግባር አፈፃፀም አኳያ ትኩረት ሊሰጠው የሚገባው ጉዳይ በየምዕራፎቹ መፈፀም ያለባቸው ተግባሮች በሙሉ ሳይንጠባጠቡና ወደሌላኛው ምዕራፍ ሳይሸጋገሩ መፈፀማቸውን በጥብቅ ዲሲፕሊን መከታተልና ችግር ሲያጋጥም በፍጥነት ማስተካከል ስራ መስራት የሚገባን መሆኑን የሚያረጋግጥ አቅጣጫ መከተል፤
- ሦስቱንም የድጋፍና ክትትል ሥራዎች ተመጋጋቢ በሆነ ሁኔታ መጠቀም፣ በጠራ የመረጃ አያያዝ የተደገፈና ውስጠ ፓርቲ ዲሞክራሲን ባረጋገጠ ትግል መፈጸሙን ማረጋገጥ ይገባል፤
- በአደረጃጀት ዘርፍ የተዘጋጀ የ2017 ዓ.ም ዕቅድ እስከ ታች (ህዋስ) ድረስ በአሉን አደረጃጀታችን የሚናበብ፣ የተቆጠረ፣ በውጤት መለካት የሚችል እና የተቀመጠውን አጠቃላይ ግብ ማሳካት የሚችል መሆኑን ማረጋገጥ ይጠይቃል። ለእያንዳንዱ ግብም የሚያስፈልግ በጀት፣ ዝርዝር ተግባራት፣ ፈጻሚ አከልና የሚፈፀምበት ጊዜን የያዘ የድርጊት መርሃ ግብር ሊቀመጥለት ይገባል። ተግባራት ሲቀመጡ ፈጻሚዎችን የሚያነቃቁና የሚከታተለውን አመራርም ተቆጥሮ የሚሰጣቸውና የሚረከባቸው መሆን አለባቸው፤
- የአባላት ምልመላችን ጥራት ማዕከል ያደረገና ለፓርቲው አቅም መሆን የሚችሉ ምሁራንን፣ ሴቶች፣ ወጣቶችን በልዩ ትኩረት መመልመል ያስፈልጋል፤
- ከሌሎች ዘርፎች ጋር በቅንጅት የሚሰሩ የፓርቲ ተግባራትን በጋራ በመቀናጀት በጋራ መሰራት ያለባቸውን በጋራ እቅድ በመመራት መፈፀም በየዘርፉ የሚሰሩት ደግሞ መረጃ የጋራ በማድረግ ላይ የተመሰረተ ጠንካራ ግንኙነት በመመስረት የፓርቲ የመፈፀም አቅም የሚያጠናክር አቅጣጫን መከተል፤

በ2017 ዓ/ም አንድም

- በዕቅድ የማይመራ፤
- በአግባቡ ያልተደራጀ፤
- በቋሚነት የማይወያይ፤
- በፓርቲው እሳቤ የማይመራ፤
- የፓርቲውን አሰራር የማይከተል፤
- በተግባር አፈጻጸም የማይመዘን አመራር፣ አባላትና አደረጃጀቶች አይኖሩም፤
- የዕለት ተዕለት ሥራዎቻችን በታቀደው መሠረት አጠናክረን መቀጠልና ውጤት የምናስመዘግብበት ዓመት መሆን አለበት፡፡ አመራርና አባላት የፖርቲውን ፕሮግራምና መተዳደርያ ደንብ፣ እሳቤዎችን፣ መርሆዎችንና እሴቶችን በአግባቡ የተገነዘቡና ራዕይ የሚጋሩ እንዲሆኑ ተከታታይ የዕለት ተዕለት ግንባታ ሥራ በጥብቅ ዲስፐሊን መሰራትን አቅጣጫ መከተል፡፡
- ለማረምና ለመገንባት የሚያስችሉ በቅቶ ማብቃት ስትራቴጅን መተግበሪያ ዋነኛ መድረኮች እንዲሆኑ ማድረግ፣ በፖርቲው አባላት ዘንድ መሰረጽ የሚገባቸውን አስተሳሰቦች በተለያየ መልኩ በድግግሞሽ አጀንዳ እንዲሆኑና እንዲሰርጹ ማድረግ የትኩረት አቅጣጫ ነው፡፡

እነዚህ ከላይ በዝርዝር የተቀመጡት የአፈፃፀም አቅጣጫዎች እንደተጠበቁ ሆኖ በልዩ ትኩረት የምንከተላቸው የአፈፃፀም አቅጣጫዎች፡-

1. ሁሉም አመራርና ፈፃሚ አካላት በተቀናጀና በተናበበ መንገድ መስራት፤
2. በየምዕራፉ መፈፀም ያለባቸው ተግባሮች ሳይንጠባጠቡ እንዲፈፀሙ ማድረግ፤
3. መሰረታዊ ለውጥ ሊያመጣ የሚችል ብስለትና ብቃት የታከለበት ውጤት ተኮር ክትትልና ድጋፍ ማድረግ፤
4. ከላይ እስከታች የተናበበ በውጤት የሚለካ፣ እንዲሁም ግቡን ለማሳካት የሚያስችሉ ተግባራት መከናወናቸውን በየምዕራፉ ማረጋገጥ፤
5. የውስጠ ዴሞክራሲን ሊያጎለብት የሚችል ጥራት ያለው መረጃ ይዞ ዴሞክራሲያዊ ትግል ማድረግ፤

## 3.2. ሪፖርትና ግብረ-መልስ

- በየወሩ ከ 24-25 ድረስ ሪፖርት በፅሑፍ ለዘርፉ መላክ አለበት፡፡

## 3.3. የመደበኛ ግምገማ መድረክ

- አደረጃጀት ዘርፍ ከመ/ድርጅት እና ህዋስ አደረጃጀት ዘርፎች ጋር በየወሩ በአካል በመገናኘት ተግባራትን በጋራ ይገመግማሉ፡፡

## 3.4. ሱፐርቪዥንና ኢንስፔክሽን

ከፓርቲዉ ጽ/ቤት ጋር በመነጋገር አደረጃጀቶች ያሉበት ሁኔታ በዓመት አራት ጊዜ ሱፐርቪዥን በማካሄድ መልካም ልምዶች ተለይተው እንዲቀመሩና እንዲሰፉ ማድረግ የሚያስችል ክትትልና ድጋፍ በማድረግ ወቅታዊና ችግር ፈቺ ግብረ-መልስ መስጠትና የታዩ ምርጥ ልምዶች ቀምሮ ማስፋት፣ ክፍተቶችን ለይቶ ለመፍታት ድጋፍ በሚመለከታቸው አመራሮች እንዲሰጥ የማድረግ ስራ ይሰራል፡፡

## 3.5. ሊያጋጥሙ የሚችሉ ችግሮችና የመፍትሔ አቅጣጫዎች

### 3.5.1. ሊያጋጥሙ የሚችሉ ችግሮች

- የስራ አቅጣጫዎች ማለትም ጥራት፣ውጤታማነት እና ተጠያቂነትን ማረጋገጥ እንደ ወሳኝ መርህ ይዞ በሁሉም ስራዎቻችን ላይ ያለመተግበር ፣ በተለመደው አግባብ ለመሄድ መፈለግ፤

- በአሰራር ላይ የተመሰረተ ጠንካራ የፓርቲ ተቋማዊ አደረጃጀት መገንባት ላይ የጋራ መግባባት በመፍጠር ወጥ የሆነ አፈፃፀም አለመኖር፤

- የአባላት መረጃ አያያዝና የመረጃ ቋት አጠቃቀም ጉድለትና የጥራት ችግር፤
- የመዋቅራችን የሥራ የተነሳሽነትና ዝግጁነት የተሟላ ሁኖ አለመገኘት፤
- በአመራር ሥርዓታችን የአስተሳሰብና የተግባር አንድነት በሚጠበቀው ደረጃ ሁኖ አለመገኘት፤
- ለዘርፉ አዲስ የሆኑ የዘርፍ አመራሮች ያሉ ከመሆኑ ጋር ተያይዞ የዘርፉን ስራዎች በተሟላ ዕውቀት የመምራት ችግር፤
- በሱፐርቪዥን ወቅት በድክመት የተለዩ ግኝቶችን ፈጥኖ የማስተካከል ውስንነት
- የዘርፉን ስራዎችና የሚሰጡ ተልዕኮዎችን ከመደበኛ ስራዎች ጋር አቀናጅቶ መምራት ላይ ያለ ውስንነት፤

### 3.5.2. የሚወሰዱ የመፍትሄ ሀሳቦች

- የሁሉም ስራችን ማዕከል እና የመጨረሻ ውጤት መለኪያ ጥራትን፣ውጤታማነት እና ተጠያቂነትን ማረጋገጥ እንዲሆን ማድረግ፤

- የፓርቲው አሰራሮችና መመሪያዎች ላይ በቂ ግንዛቤ መፍጠር፣ በተግባር አፈፃፀም አሰራሮችን በመረዳት መሰራታቸውን መከታተልና መደገፍ፤
- ለአመራሩ በቂ መግባባት ሊፈጥር የሚችል እቅድ ኦሬንቴሽን መስጠትና መግባባት ላይ በማድረስ ወደ ተግባር ማስገባት፤
- መደበኛ የዘርፍ ስራዎችንና ሌሎች ስራዎችን አቀናጅቶ መስራት፤
- የአባላት መረጃ በጥራት አሟልቶ መያዝ የእያንዳንዱን አባል መረጃ በዳታ ቤዝ ውስጥ ማስገባትና አጠቃቀሙን ማዘመን፤
- በየደረጃው ካሉት ኃላፊዎች ጋር ውይይት በማድርግ በድክመት የተለዩ ግኝቶችን ፈጥኖ እንዲስተካከሉ ማድራግ፤
- የአመራር ሥርዓታችን የአስተሳሰብና የተግባር አንድነት ማጠናከር፤
- በየምዕራፉ አመራርንና ፈጻሚ አካላትን የሚመጥን በግምገማዊ ስልጠና በመስጠት የማብቃት ወዘተ… ስራዎች በመስራት ቸግሮችን መፍታት፤

**ማጠቃለያ**

እንደ ዘርፍ በ2017 በጀተ አመት የፓርቲዉን መሪ እቅድ መነሻ በማድረግ የዘርፉን መሬ እቅድ አቅደን ወደ ተግባር የገባን መሆኑ ይታወቃል በርካታ ዉጤቶችም መተዋል ይሁን እንጀ በበጀት አመቱ መከናወን ያለባቸዉን ተግባራት ከክ/ከተማ ዘርፍ ጋር በመናበብ የተከለሰ እቅድ አቅደን ወደ ተግባር መግባት አስፈላጊ በመሆኑ ሁሉም ከላይ በዝርዝር የታቀዱ እቅዶችን ዉጤታማ ለማድረግ የፓርቲያችን መዋቅር የወረዳዉን ንዋሪ በማስተባበር ከምንጊዜዉም በላይ በመተባበር እና በቅንጅት መስራት ያስፈልጋል ፡፡

## IV የአደረጃጀት ዘርፍ 2017 ግቦች፣ ዋና ዋና ተግባራትና ቁልፍ የአፈጻጸም አመላካቶች

| የአደረጃጀት ዘርፍ 2017 ግቦች፣ ዋና ዋና ተግባራትና ቁልፍ የአፈጻጸም አመላካቾች | | | | | | | | | | | | | | |
|---|---|---|---|---|---|---|---|---|---|---|---|---|---|---|
| 1. አደረጃጀት አሰራርን በማዘመንና ተግባራዊ በማድረግ የፓርቲዉን ተቋማዊ ጥንካሬ ማረጋገጥ ( ክብደት 22.5) | | | | | | | | | | | | | | |
| ተቁ | ስትራቴጂክ ግቦች፣ ዋና ዋና ተግባራ | 2017 ዕቅድ | የዓመት ዒላማዎች | | | | | | | | | | | |
| | | | ሐም | ነሐሴ | መስከ | ጥቅመ | ህዳር | ታህሳ | ጥር | የካቲ | መጋ | ሚያ | ግን | ሰኔ |
| 1.1 | በግልፅ የተልዕኮ ስኬት ላይ የተመሰረተ የምደባ ስርዓት በመዘርጋት እና የምዘናና እውቅና ስርዓት እውን በማድረግ የፓርቲ ተቋማዊ ጥንካሬ ማሳደግ ( ክብደት 6) | | | | | | | | | | | | | |
| 1.1.1 | ብቃት ያለው የአመራር ምደባ (ክብደት 1) | በቁ 33 | | | 33 | | | | | 33 | | | | |
| 1.1.2 | የአመራር ምዘና (ክብደት 1) | 99% | | 99% | | | | | | 99% | | | | |
| 1.1.3 | የአባል የምዘና (ክብደት 1) | 85% | | 85% | | | | | | 85% | | | | |
| 1.1.4 | የመሠረታዊ ድርጅት ምዘና (ክብደት 1) | 100% | | 100 % | | | | | | 100 % | | | | |
| 1.1.5 | የህዋስ ምዘና (ክብደት 1) | 100% | | 100 % | | | | | | 100 % | | | | |
| 1.16 | የተሻለ አፈፃፀም ላላቸው አካላት እውቅና መስጠት (ክብደት1) | በቁጥር 1 | | 1 | | | | | | | | | | |

| | | | | | | | | | | | | | | |
|---|---|---|---|---|---|---|---|---|---|---|---|---|---|---|
| 1.2 | **የፓርቲውን አደረጃጀትና አሰራሮች በማዘመን የፓርቲውን ተቋማዊ ጥንካሬ ማሳደግ (ክብደት 6.5 )** | | | | | | | | | | | | | |
| 1.2.1 | **ጠንካራ የፓርቲ ተቋማዊ አደረጃጀት መፍጠርና መገንባት (ክብደት 3 )** | | | | | | | | | | | | | |
| 1.2.1.1 | መሰረታዊ ድርጅቶች አደረጃጀት ማጠናከር (ክብደት 1) | 100% | | | 100% | | | 100% | | | 100% | | | 100 % |
| 1.2.1.2 | የህዋስ አደረጃጀት ማጠናከር (ክብደት 1) | 100% | | | 100% | | | 100% | | | 100% | | | 100 % |
| 1.2.2 | **በየደረጃው ያለው አስተባባሪና አመራር ኮሚቴ፣ የአደረጃጀቶች አመራሮች፣ መሰረታዊ ድርጅት ኮንፈረንስ፣ የሕዋስ ውይይት በተከታታይ ቋሚ ግንኙነት ጊዜያቸውን ጠብቀው ግምገማና ውይይት ማካሄዳቸውን ማረጋገጥ (ክብደት 3 )** | | | | | | | | | | | | | |
| 1.2.3.1 | የአስተባባሪ ኮሚቴ የግንኙነትና የግምገማ ስርዓትን ማጠናከር (ክብደት 0.5) | በቁ 48 | 4 | 4 | 4 | 4 | 4 | 4 | 4 | 4 | 4 | 4 | 4 | 4 |
| 1.2.3.2 | የፓርቲ ኮሚቴ ውይይትና ግምገማ (ክብደት 0.5) | በቁ 48 | 4 | 4 | 4 | 4 | 4 | 4 | 4 | 4 | 4 | 4 | 4 | 4 |
| 1.2.3.3 | የአደረጃጀት አመራሮች የግንኙነትና የግምገማ ስርዓት ማጠናከር (ክብደት 0.5) | በቁ 12 | 1 | 1 | 1 | 1 | 1 | 1 | 1 | 1 | 1 | 1 | 1 | 1 |
| 1.2.3.4 | የመሰረታዊ ድርጅት ኮንፈረንስ (ክብደት 0.5) | በቁ 4 | | | 1 | | | 1 | | | 1 | | | 1 |
| 1.2.3.5 | የሕዋስ ውይይት ማካሄድ (ክብደት 0.5) | በቁ 12 | | | | | | | | | | | | |

| | | | | | | | | | | | | | | |
|---|---|---|---|---|---|---|---|---|---|---|---|---|---|---|
| 1.2.3.6 | ለአቅም ግንባታና ስልጠና ተግባራት የሚዘጋጁ አመራር በግልፅ መስፈርት መለየት (ክብደት 0.5) | በቁ 33 | | | 33 | | | | 33 | | | | | 33 |
| **1.2.4** | **የፓርቲ አደረጃጀቶች፣ አመራሮች፣ አባላት፣ መረጃ በቴክኖሎጂ የተደገፈ፣ የሚተዳደር እንዲሆን ማድረግ (ክብደት 1.5 )** | | | | | | | | | | | | | |
| 1.2.4.1 | ጥራትና ብቃት ያለው የአመራርና አባላት መረጃን ወደ ዳታ ቤዝ ማስገባት (ክብደት 0.5) | 100% | | | 100% | | | 100% | | | 100% | | | 100 % |
| 1.2.4.2 | መረጃን በየወቅቱ በማጥራት የመረጃ ተአማንነት ማረጋገጥ (ክብደት 0.5 ) | በቁ 4 ግዜ | | | 1 | | | 1 | | | 1 | | | 1 |
| 1.2.4.3 | የአባላት መታወቂያ ዲጂታል የተደረገዉን መሰራጫት (ክብደት 0.5 ) | በቁ 2 | | | 1 | | | | | | | | 1 | |
| **1.3** | **በፓርቲው መተዳደሪያ ደንብና አሠራር መሰረት ነባሩን አመራርና አባሉን በማጥራት አዳዲስ አባላት ምልመላ በማድረግ የፓርቲውን መሠረት ማስፋት (ክብደት 4)** | | | | | | | | | | | | | |
| 1.3.1 | አባላት ማጥራት (ክብደት 1) | 100% | | 100 % | | | | | | 100 % | | | | |
| 1.3.2 | አመራርን ማጥራት ( ክብደት 1) | 100% | | 100 % | | | | | | 100 % | | | | |

| | | | | | | | | | | | | | | |
|---|---|---|---|---|---|---|---|---|---|---|---|---|---|---|
| 1.3.3 | ምሁራን፣ ተፅህኖ ፈጣሪ ሰዎች እና በለህብት ላይ ያተኮረ ምልመላ (ክብደት 1.5) | 159 | | 27 | | 22 | | 22 | | 22 | 22 | | 22 | 22 |
| 1.3.4 | የተመለመሉትን ማብቃት/ማወያየት (ክብደት 0.5) | 100% | | 100 % | | 100 % | | 100% | | 100 % | 100% | | 100 % | 100 % |
| **1.4** | **በመላ አባላቱ ዘንድ ተቀባይነት ያለው በየደረጃው የውስጥ ምርጫ በማካሔድ የፓርቲውን ዴሞክራሲያዊነትና አመራር ማረጋገጥ ( ክብደት 2 )** | | | | | | | | | | | | | |
| 1.4.1 | የውስጠ ፓርቲ ምርጫ በማካሄድ የፓርቲን ጥንካሬ ማጎልበት (ክብደት 1) | 70% | | | 70% | | | 70% | | | 70% | | | 70% |
| 1.4.2 | አካታችነትና ተመጣጣኝ ውክልናን እውን ማድረግ አመራር ማጠናከር (ክብደት 1) | 100% | | 100 % | | | 100 % | | | 100 % | | | 100 % | |
| **1.5** | **የሀገሪቱን ፖለቲካዊ፣ ኢኮኖሚያዊና ማህበራዊ ፖሊሲዎችን በብቃት ማቀድና መፈፀም የሚችል አመራር በየደረጃው ማፍራትና ማብቃት(ክብደት 2)** | | | | | | | | | | | | | |
| 1.5.1 | በመስፈርቱ መሰረት ተተኪ አመራር መለየትና ማጠናከር (ክብደት 1) | በቁ 474 | | | | 94 | | 95 | | 95 | | 95 | | 95 |
| 1.5.1 | ኮር አመራር መለየትና ማጠናከር (ክብደት 1) | በቁ 19 | | | | | 3 | 4 | 2 | 2 | 2 | 2 | 2 | 2 |

ሠንጠረዥ1 የግንባር ቀደም፣ ተተኪና ኮር አመራር ምልመላ ዕቅድ

| ተቁ | ወረዳዎች 01 | ግንባር ቀደም አባላት | | | ተተኪ አመራር | | | ኮር አመራር | | |
|---|---|---|---|---|---|---|---|---|---|---|
| | | ወ | ሴ | ደምር | ወ | ሴ | ድምር | ወ | ሴ | ድምር |
| | | **2344** | **3277** | **5621** | **237** | **237** | **474** | **12** | **7** | **19** |
| 1 | ወጣት ሊግ | 1240 | 1149 | 2389 | 210 | 10 | 220 | | | |
| 2 | ሴት ሊግ | | 1918 | 1918 | | 210 | 210 | | | |
| 3 | መኖሪያ | 749 | | 749 | 4 | 4 | 8 | | | |
| 4 | ጥቃቅን | 120 | 104 | 224 | 10 | | 10 | | | |
| 5 | ት/ቤት | 30 | 20 | 50 | 3 | 3 | 6 | | | |
| 6 | ቢሮ | 156 | 86 | 242 | 10 | 10 | 20 | 14 | 5 | 19 |
| 7 | ባለሀብት | 20 | | 20 | | | | | | |
| 8 | ነጋዴ | 20 | | 20 | | | | | | |
| 9 | አርሶ አደር | 9 | | 9 | | | | | | |
| ድምር | | 2344 | **3277** | **5621** | **237** | **237** | **474** | **14** | **5** | **19** |

| የ2017 የወረዳ 01 የተቋማትና ማህበራዊ መሰረት ዓመታዊ ዕቅድ ድልድል | | | | | | | | | | |
|---|---|---|---|---|---|---|---|---|---|---|
| ተቁ | ወረዳ 01 | ከተፅዕኖ ፈጣር ወጣቶች | | | ከምሁራን | | | ከበለሃብቶች | | |
| | | ወ | ሴ | ደምር | ወ | ሴ | ድምር | ወ | ሴ | ድምር |
| | | **33** | **32** | **65** | **43** | **41** | **84** | **7** | **3** | **10** |
| **1** | **ወጣት ሊግ** | 15 | 10 | 25 | 20 | 15 | 35 | | | |
| **2** | **ሴት ሊግ** | | 20 | 20 | | 15 | 15 | | | |
| **3** | **መኖሪያ** | 3 | | 3 | 2 | | 2 | 7 | 3 | **10** |
| **4** | **ጥቃቅን** | 5 | | 5 | 1 | 1 | 2 | | | |
| **5** | **ት/ቤት** | 6 | 1 | 7 | 10 | 5 | 15 | | | |
| **6** | **ቢሮ** | 4 | 1 | 5 | 10 | 5 | 15 | | | |
| | **ድምር** | **33** | **32** | **65** | **43** | **41** | **84** | **7** | **3** | **10** |

| የ2017 የወረዳ 01 የተቋማትና ማህበራዊ መሰረት ዓመታዊ ዕቅድ ድልድል | | | | | |
|---|---|---|---|---|---|
| ተ.ቁ | ወረዳ 01 | ግንባር ቀደም መ/ድርጅት | | ሞዴል መ/ድርጅት (በ25%) | |
| | | ያለ መ/ድርጅት ብዛት | ግንባር ቀደም እቅድ | ያለ መ/ድርጅት ብዛት | ሞዴል እቅድ |
| | | 36 | 32 | 36 | 9 |
| 1 | ወጣት ሊግ | 15 | 14 | 15 | 4 |
| 2 | ሴት ሊግ | 12 | 11 | 12 | 3 |
| 3 | መኖሪያ | 5 | 3 | 5 | 1 |
| 4 | ጥቃቅን | 1 | 1 | 1 | |
| 5 | ት/ቤት | 1 | 1 | 1 | |
| 6 | ቢሮ | 2 | 2 | 2 | 1 |
| | ድምር | 36 | 32 | 36 | 9 |

2017 የወረዳ 01 የተቋማትና ማህበራዊ መሰረት ዓመታዊ ዕቅድ ድልድል

| ተቁ | ወረዳ 01 | ህዋሳት | ሞዴል ህዋሳት | |
|---|---|---|---|---|
| | | ያለ ህዋሳትብዛት | ያለ ህዋሳትብዛት 2016 ሞዴል ህዋስ የሆኑትን መነሻ ማድረግ | ሞዴል ህዋስ (በ20%) እቅድ |
| | | **223** | **29** | 45 |
| 1 | **ወጣት ሊግ** | 95 | 12 | 19 |
| 2 | **ሴት ሊግ** | 78 | 10 | 16 |
| 3 | **መኖሪያ** | 29 | 2 | 6 |
| 4 | **ጥቃቅን** | 7 | 2 | 1 |
| 5 | **ት/ቤት** | 3 | 1 | 1 |
| 6 | **ቢሮ** | 11 | 2 | 2 |
| | **ድምር** | **223** | **29** | **45** |

## የ2017 የወረዳ 01 የተቋማትና ማህበራዊ መሰረት ዓመታዊ ዕቅድ ድልድል

| ተቁ | ወረዳ 01 | አባላት | | ሞዴል አባላት | |
|---|---|---|---|---|---|
| | | ያለ አባላት ብዛት | ግንባር ቀደም አባላት እቅድ | የአባል ብዛት | ሞዴል አባል እቅድ(15%) |
| | | **8030** | ***5621*** | **8030** | **1204** |
| | **ወጣት ሊግ** | 3413 | 2389 | 3413 | 512 |
| | **ሴት ሊግ** | 2740 | 1918 | 2740 | 411 |
| | **መኖሪያ** | 1070 | 749 | 1070 | 160 |
| | **ጥቃቅን** | 320 | 224 | 320 | 48 |
| | **ት/ቤት** | 71 | 50 | 71 | 11 |
| | **ቢሮ** | 345 | 242 | 345 | 52 |
| | **ነጋዴ** | 29 | 20 | 29 | 4 |
| | **አርሶአደር** | 13 | 9 | 13 | 2 |
| | **ባለሀብት** | 29 | 20 | 29 | 4 |
| **ድምር** | | **8030** | ***5621*** | **8030** | **1204** |